# የኢትዮጵያ ሕገ መንግሥት ጉባኤ

## ቃለጉባኤ

## ጥራዝ

## 1

ጥቅምት 19-1987 ዓ.ም

አዲስ አበባ

## ማውጫ

## ጥራዝ 1

ጥቅምት 18 ቀን 1987 ዓ.ም ከሰዓት በኋላ የተጀመረው የኢትዮጵያ ሕገ መንግሥት ጉባኤ ጊዜያዊ የአመራር አባላትን እስኪመርጥ ድረስ በአቶ ዳዊት ዮሐንስ የኢትዮጵያ የሽግግር መንግሥት የተወካዮች ምክር ቤት አባልና የሕገ መንግሥት ኮሚሽን ፀሐፊ የተመራ ሲሆን አጀንዳውም ፣

የጉባኤው ቋሚ የአመራር አባላት የሚያስመርጥ ጊዜያዊ ኮሚቴ መምረጥ ይቻል ዘንድ የጉባኤውን ጊዜያዊ ሊቀመንበር መመረጥ ፣

የሚል መሆኑን ክቡር አቶ ዳዊት ዮሐንስ አጀንዳውን ካስተዋወቁ በኋላ የሚመረጠው የጉባኤው ጊዜያዊ ሊቀመንበር ተግባርና ኃላፊነት ከጉባኤው ጊዜያዊ አመራር አባላት መካከል እንዲመረጡ ማድረግ እንደሆነ ጠቁመው ጊዜያዊ ሊቀመንበሩ ሆነ ቀጥሎ የሚመረጡ ጊዜያዊ የጉባኤው አመራር አባላት ምርጫ እጅ በማውጣት እንደሚከናወን ገልጸዋል ::

አያይዘውም ቋሚ የጉባኤው አመራር አባላት ግን በፓርላሜታዊ ምርጫ ሥርዓት መሠረት ምርጫው በሚስጥር እንደሚካሄድ ገልጸው ጊዜያዊ ሊቀመንበሩን ለመምረጥ ሦስት ያህል ዕጩዎች ከመጠቆማቸው በፊት የተለየ አስተያየት ካለ ማቅረብ እንደሚቻል አሳስበዋል ::

በዚህም መሠረት ከክልል አንድ አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ የጊዜያዊ ሊቀመንበሩ ተግባርና ኃላፊነት የጊዜያዊ ጉባኤው አመራር አባላት ማስመረጥ ብቻ ሳይሆን የሕግ መንግሥቱ ሂደት እና የሕገ መንግሥቱ ጉባኤ አባላት ምርጫ ዲሞክራሲያዊነት እንዲገመገም ማድረግ ጭምር መሆን እንዳለበት ገልጸዋል ::

አቶ ዳዊት ዮሐንስ የሀሳቡን ጠቃሚነት በማመን በሕገ መንግሥት ጉባኤ መክፈቻ ወቅት ስለሕግ መንግሥቱ አረቃቀቅና ስለሕገ መንግሥት ጉባኤ አባላት ምርጫ በአቶ ክፍሌ ወዳጆ የኢትዮጵያ የሽግግር መንግሥት የተወካዮች ምክር ቤት አባልና የሕገ መንግሥት ኮሚሽን ሰብሳቢ እንዲሁም በአቶ ከማል በድሪ የማዕከላዊ ጠቅላይ ፍርድ ቤት ፕሬዚዳንትና የብሔራዊ ምርጫ ቦርድ ሰብሳቢ ሰፊ ማብራሪያ መሰጠቱን ፣ የምርጫ ቦርድ ሪፖርትም ለያንዳንዱ አባል መታደሉን ጠቁመው የረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ዝግጅት ሂደትና የሕግ መንግሥት ጉባኤ አባላት ምርጫን ዲሞክራሲያዊነት በቅድሚያ መገምገምና የጉባኤውን ቋሚ የአመራር አባላት የሚያስመረጥ ጊዜያዊ ኮሚቴ መምረጥ እንደሚገባ ያቀረቡት ሀሳበ ጉባኤው ተቀብሎታል ::

በሌላ በኩል ጊዜያዊ አመራሩን የሚያስመርጠው ሰው አንድ ከሚሆን ሦስት ሰዎች እንዲሆኑና ሥራውን በጋራ እንዲያከናውኑ የተለያዩ የጉባኤው አባላት ያቀረቡት ሀሳብ ጉባኤው ተቀብሉ 5 ሰዎች እንዲጠቆሙ ወሰኗል ::

በዚህም መሠረት ፣

1. ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ፣ የማስታወቂያ ሚኒስትርና የጉባኤው አባል
2. አቶ አዲሱ ለገሠ ፣ የክልል ሦስት ፕሬዚዳንትና የጉባኤው አባል
3. አቶ አባተ ኪሾ ፣ የደቡብ ኢትዮጵያ ብሔር/ብሔረሰቦችና ሕዝቦች ክልል ፕሬዚዳንትና የጉባኤው አባል
4. ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን : የውጭ ኢኮኖሚ ትብብር ሚኒስትርና የጉባኤው አባል
5. ዶ/ር አድማሱ ለማ : የጉባኤው አባል

ተጠቁመው ራሳቸውን ተራ በተራ ለጉባኤው አባላት ካስተዋወቁ በኋላ ድምፅ ተሰጥቶ ፣

| | | |
|---|---|---|
| 1. | ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ | 474 ድምፅ |
| 2. | አቶ አዲሱ ለገሠ | 501 ድምፅ |
| 3. | አቶ አባተ ኪሾ | 491 ድምፅ |
| 4. | ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን | 24 ድምፅ |
| 5. | ዶ/ር አድማሱ ለማ | 9 ድምፅ |

አግኝተዋል :: ከፍተኛ ድምፅ ያገኙት ፣

ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ፣ አቶ አዲሱ ለገሠ ፣ አቶ አባተ ኪሾ የሥራ ክፍፍል አድርገው ፣

1. ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ፣ የጉባኤው ጊዜያዊ ሊቀመንበር
2. አቶ አዲሱ ለገሠ ፣ የጉባኤው ጊዜያዊ ፀሐፊ
3. አቶ አባተ ኪሾ ፣ የጉባኤው ጊዜያዊ ም/ ፀሐፊ

በመሆን መድረኩን ተረክበዋል ::

በመጀመሪያ የጉባኤው ጊዜያዊ ሊቀመንበር አጀንዳዎቹ ፣

በመጀመሪያ የጉባኤው ጊዜያዊ ሊቀመንበር አጀንዳዎቹ ፣

1. የሕገ መንግሥት ጉባኤ ቋሚ አመራር የሚያስመርጡ ሰዎችን መምረጥ
2. የረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ዝግጅት ሂደትና የሕገ መንግሥት ጉባኤ አባላት ምርጫን መገምገም ፣



የሚሉ እንደሆነ ገልጸው በመጀመሪያ በተራ ቁጥር 2 አጀንዳ ላይ ውይይቱ ከመቀጠሉ በፊት ጉባኤው በሕገ መንግሥቱ ዝግጅት ሂደትና በምርጫ ው ላይ ውይይት ይካሄድ አይካሄድ የሚለው ላይ እንዲወስን አሳስበዋል ::

በዚህም መሠረት ከክልል 1 አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ የሕገ መንግሥቱ አረቃቀቅ ሂደት ሕዝቡን ያሳተፈ መሆኑ አንዱ ጉዳይ መሆኑን ጠቁመው በጉባኤው የሚሳተፈው ሰው ሁሉ በሕዝብ ተመርጦ የመጣ ስለሆነ የሂደቱ ዲሞክራሲያዊነት ሳያረጋግጥ ቋሚ አመራር አይመረጥም ከሚል መነሻ ቀደም ሲል ሀሳብ እንዳቀረቡ አስረድተዋል ::

አያይዘውም በመጀመሪያ በሕገ መንግሥቱ አረቃቀቅ ሂደት ዲሞክራሲያዊነት ላይ ቀጥሎ በምርጫው ክንውን ላይ ውይይት ከተደረገ በኋላ ጉባኤው በእነዚህ ዲሞክራሲያዊ መሆን አለመሆን ላይ ወስኖ አስመራጭ ኮሚቴውን መምረጥ እንዳለበት አሳስበዋል ::

በሌላ በኩል ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ የቀረበውን ሀሳብ የሚቃወም ካለ ሀሳቡን ማቅረብ እንደሚችል በጠየቁት መሠረት ከክልል 14 ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ስለምርጫው ሂደት በጋዜጦች ደጋግመው የጻፉ መሆናቸውን ጠቁመው መድገሙ እንደማይገባ አብራርተዋል ::

አያይዘውም የሕዝብ ተሳትፎ እንዳልነበረ ፣ ለምሳሌም 17,000 ያህል ነዋሪዎች ባሉበት ቀበሌ ብዙ ሺህ የጥሪ ወረቀት ተልኮና በድምፅ ማጉያ ተነግሮ የመጣው ሰው 119 ብቻ እንደሆነ : 5000 ነዋሪ ያለበት ቀበሌ ለስብሰባ የመጣው 32 ሰው ብቻ እንደነበር ፣ ሰው ያልመጣባቸው ቀበሌዎችም እንደነበሩ ፣ የቀበሌ ሊቀመንበር ሚስቱና ልጆቹ ይዞ በመምጣት ሕዝቡ ተሳትፏል መባል እንደሌለበት ገልጸዋል ::

ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳም በመጀመሪያ በጉዳዩ ላይ እንወያይበት ወይንስ እንዲሁ እንወስን በሚለው ላይ መወሰን እንደሚገባ በጠየቁት መሠረት የጉባኤው አባላት ውይይቱ እንዲቀጥል ተስማምተዋል :: በሌላ በኩል ግን አንድ የጉባኤው አባል የጉባኤው ቋሚ አመራር ከተመረጠ በኋላ በጉዳዩ ላይ ብንወያይ የሚል ሀሳብ ቢያቀርቡም በጉባኤው ተቀባይነት አላገኘም ::

በመቀጠልም ሰብሳቢው በመጀመሪያ የሕገ መንግሥት ማርቀቅ ሂደት ዲሞክራሲያዊ ነበር የሚለውን ሀሳብ የሚደግፉ ሰዎች አስተያየታቸውን እንዲያቀርቡ ባሳሰቡት መሠረት ከክልል 5 አቶ መሀሙድ ድሪር ጌድ ረቂቅ ሕገ መንግሥቱ የማዘጋጀት ሂደት ከኢትዮጵያ ሶማሌ ዲሞክራሲያዊ ድርጅት አቋም ረቂቅ ሕገ መንግሥቱ በኢትዮጵያ ለመጀመሪያ ጊዜ ዲሞክራሲያዊ እንደሆነ ፣ ከዚህ በፊት

በአፄ ኃይለሥላሴ ዘመነ መግሥት የተጻፈው ሕገ መንግሥት ይህ ይሁንላችሁ ተብሎ የተሰጠ በይዘቱም በትርጉም ኢ-ዲሞክራሲያዊ የሆነና ሕዝቡ ያልተሳተፈበት እንደነበር ፣ ቀጥሎም የደርግ ኢሠፓ ሥርዓት ኃላፊነት አለብኝ በሚል ከኮሚኒስት የምሥራቅ አገሮች የተቀዳ ሕገ መንግሥት ለኢትዮጵያ አጽድቋል ቢባልም ኢ-ዲሞክራሲያዊ እንደነበር ፣ አሁን የተቀረጸው ሕገ መንግሥት ግን መጀመሪያ ፅንሰ ሐሳቦች ብቻ ለሕዝብ ቀርበው ሕዝቡ ስለሕገ መንግሥቱ አደረጃጀት ፣ ስለሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ ፣ ስለሃይማኖቶች እኩልነት ፣ ስለቋንቋዎች ወ.ዘ.ተ... ተነጋግሮ ማዳበሩን ፣ የተለያየ አመለካከት ካላቸው የፖለቲካ ድርጅቶች ፣ ከሃይማኖት መሪዎች ፣ ከሕግ ባለሙያዎች ፣ ከሴቶች ወ.ዘ.ተ... የተውጣጡ አባላት ያሉበት አካል የሕዝብ አስተያየት መሠረት በማድረግ ያረቀቀው እንደሆነ አብራርተዋል ::

አያይዘውም የሕገ መንግሥት ኮሚሽን የሃይማኖት መሪዎችን ሴቶችን ፣ የአገር ሽማግሌዎችን ፣ በአጠቃላይ ደግሞ ሕዝቡን / ዘላኑ ጨምሮ / በማወያየት ያረቀቀው ስለሆነ የተወካዮች ምክር ቤትም ከ12 ቀናት ተወያይቶበት እንዳሳለፈው አስገንዝበዋል ::

የእነዚህን ሁሉ አመለካከት በዲሞክራሲያዊ መንገድ አካትቶ ከመቅረቡም ባሻገር በዕለቱ የሕገ መንግሥት ጉባኤው ይህንን ረቂቅ ሕገ መንግሥት የማፅደቅ ወይም የማሻሻል ወይም ይህን በመተው አዲስ ሕገ መንግሥት የማርቀቅ መብት እንዳለው በፕሬዚዳንት መለስ ዜናዊ መግለጹን አብራርተው በዲሞክራሲያዊነቱ ላይ ሊሰመርበት እንደሚገባ አስገንዝበዋል ::

በተጨማሪም ከክልል 4 የተወከሉት አቶ ኩማ ደመቅሳ ሕዝቡ ከፅንሰ ሐሳቡ ጀምሮ በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ላይ ውይይት በማካሄድ ይወክሉኛል የሚላቸውን በነፃ ለመምረጥ እንዲችል መብቱ ስለተረጋገጠለት ሕገ መንግሥቱ ዲሞክራሲያዊ እንደሆነ ፣ በሕገ መንግሥት ጉባኤ መከፈቻ ወቅት በኢትዮጵያ ብሔራዊ ምርጫ ቦርድ ሰብሳቢ ሪፖርት ላይ ለመምረጥ ከተመዘገበው ሕዝብ ውስጥ 87.6% እንደመረጠ መጠቀሱ የሕዝቡን ተሳትፎ እንደሚያረጋግጥና እርሳቸው በተመረጡበት አካባቢ 90% ያህል ሕዝብ በምርጫው እንደተሳተፈና ይህም የሆነው አሠራሩ ዲሞክራሲያዊ በመሆኑ እንደሆነ ፣ ተቃዋሚዎችም ለመወዳደርና ሀሳባቸውን በነፃ ለመግለጽ እንደቻሉ እንዲሁም የተለያየ አመለካከት ያላቸው ሰዎች ለሕገ መንግሥት ጉባኤ አባልነት ተወክለው እየተሳተፉ መሆናቸውን ጠቁመው የሕገ መንግሥቱ አረቃቀቅ ሂደት ዲሞክራሲያዊ መሆኑን ገልጸዋል ::



በማስከተልም ሊቀመንበሩ የሕገ መንግሥቱ የማርቀቅ ሂደት እንዲሁም የምርጫው ሂደት ዲሞክራሲያዊ እንዳልሆነ የሚገልጹ ወገኖች ሀሳባቸውን እንዲያቀርቡ ያሳሰቡ ሲሆን በዚህም መሠረት ከክልል 14 አቶ ዳንኤል በላይነህ በአፄ ኃይለሥላሴ ዘመነ መንግሥት የነበረው ሕገ መንግሥት እንደሰጦታ የሚታይ በደርግ ዘመን ወቅትም የነበረው ደግሞ የኢትዮጵያ ሠራተኞች ፓርቲን የሚያንጸባርቅ ስለነበረ በሁለቱም ዘመነ መንግሥታት የነበሩ ሕገ መንግሥቶች ዲሞክራሲያዊ እንዳልነበሩ አውስተው የአሁን ሕገ መንግሥትም ከቀድሞዎቹ ምን ያህል የተሻለ እንደሆነ ማየት እንደሚያስፈልግ በመጠቆም ባደረጉት ገለጻ ረቂቅ ሕገ መንግሥቱን የሕገ መንግሥት ኮሚሽን ከዚያም የተወካዮች ምክር ቤት ተወያይቶበት ለሕዝብ የቀረበ ቢሆንም ሕዝቡ አንድ ቀን ብቻ ተወያይቶ ሀሳብ እንዲሰጥ ስለተደረገና ይህ 106 አንቀጾች ያካተተው ሕገ መንግሥት ከሕዝቡ የትምህርት ደረጃ አኳያ አንድ ቀን ብቻ እንዲወያይበት መደረጉ በቂ ስላልሆነ እንደገና ለሕዝብ እንዲቀርብ የሚል አስተያየት ሰንዝረዋል ::

እንዲሁም ሌላው ከክልል 14 የተወከሉት ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ በቀበሌ ተመራጮች አማካይነት የተካሄደው የማወያየትና የማሸነፍ ተግባር በትክክል እንዳልተከናወነና በተወካዮች ምክር ቤት በተካሄደው ውይይት የምክር ቤቱ ሰብሳቢ ክርክር ውስጥ ስለገቡ ትክክለኛ አመራር እንዳልነበረ ጠቁመው የሕገ መንግሥት ጉባኤው ኢትዮጵያን ስለሚወክል ለኢትዮጵያ ሕዝብ መቆም እንደሚያስፈልግ ጠቅሰዋል ::

ከዚያም ሰብሳቢው ሕገ መንግሥቱን የማርቀቅና የሕገ መንግሥት ጉባኤ አባላት ምርጫ ሂደት ዲሞክራሲያዊ አልነበረም የሚል ሀሳብ ካለ እንዲቀርብ ቢያሳስቡም ምንም ሀሳብ ባለመቅረቡ ሂደቱ ዲሞክራሲያዊ ነበር የሚል ሀሳብ ካለ ሀሳቡን እንዲያቀርብ ጠይቀዋል ::

በዚህም መሠረት ከክልል 1 የተወከሉት አቶ አለምሰገድ ገ/አምላክ የሕገ መንግሥት ኮሚሽን ሲቋቋም በተወካዮች ምክር ቤት አባል ከነበሩትና አባል ካልነበሩት ድርጅቶች በኮሚሽኑ ተሳትፎ እንዲኖራቸው ጥረት መደረጉንና አንዳንዶቹ ድርጅቶች ግን አኩርፈው በመውጣት ሊያደርጉት የሚችሉትን አስተዋፅኦ ሳያከናውኑ መቅረታቸውን ፣ ኮሚሽኑ ከተቋቋመ በኋላ የራሱ አቋም ሳይወስድ ሊነሱ የሚችሉ የተለያዩ አማራጭ ሀሳቦችን ወደሕዝቡ ማውረድና የረቂቅ ሕገ መንግሥቱን ሀሳብ ያመነጨው ሕዝቡ ሰፊና ጥልቅ ውይይት በማድረግ መሆኑን፣ ከዚያም ኮሚሽኑ የቀረበለትን የሕዝብ ሀሳብ ሙያዊ አስተዋፅኦ በማድረግ

የሕገ መንግሥት ቅርፅ አስይዞ በማዘጋጀት ለተወካዮች ምክር ቤት በማቅረብ ምክር ቤቱ ሰፊና ጥልቀ ውይይት አድርጎበት ተመልሶ ለሕዝቡ እንደቀረበ ፣ ይህም የተደረገው ሕዝቡ የሕገ መንግሥቱን መሠረታዊ ነጥቦች ተረድቶ ሀሳቡን ለማንጸባረቅ የሚያስችሉት ተወካዮችን ለመምረጥ እንዲችል እንጂ በ106 አንቀጾች ላይ በዝርዝር የሚወያይባቸው ግን ሕዝቡ የመረጠው የሕገ መንግሥት ጉባኤው መሆኑን አስገንዝበዋል ::

እያይዘውም በቀበሌ ደረጃ የተካሄዱ ውይይቶች የፆታ ፣ የዕድሜና የሃይማኖት ልዩነት ሳይፈጠር ሁሉንም ያካተተ የነበረ ሲሆን ወይይቶቹ ጠንካራና ደካማ ጎን እንደነበራቸው ፣ ስለሆነም በቀበሌ ደረጃ የተካሄደው ውይይት በቂ አለመሆኑን የሕገ መንግሥት ኮሚሽን በመገንዘብ የተለያዩ ግለሰቦች ፣ የሃይማኖት ተወካዮች ፣ ያገር ሽማግሌዎችና ሴቶችን በማወያየት ጥያቄዎችን በሕገ መንግሥቱ ለማካተት ከፍተኛ ጥረት መደረጉን ፣ በሌሎች አገሮች ያለው አሠራር ሲታይ ግን ለምሳሌም በአሜሪካ የብዙ ዓመት ልምድ ስላለ ለንፅፅር ማቅረብ ባይቻልም የአሜሪካ ሕገ መንግሥት በተወሰኑ ሰዎች ሲረቀቅ ሕዝብ እየተረቀቀ መሆኑን እንኳን እንደማያውቅ ፣ በቅርቡ በራሺያ እንደታየውም በአገሪቱ ፕሬዚዳንት አማካሪዎች የተረቀቀውን ሕገ መንግሥት ሕዝቡ መደገፉን ወይም አለመደገፉን ብቻ ተጠይቆ ማፅደቁን ፣ በአገራችን ግን ሕዝቡ ዲሞክራሲያዊ በሆነ መንገድ ተወያይቶበት አቋሙን በግልጽ በማስታወቅ የሕገ መንግሥት ጉባኤ እንዲመርጥ በመደረጉ የሕገ መንግሥት ማርቀቅ ሂደት ዲሞክራሲያዊ እንደሆነ ጠቅሰዋል ::

እንዲሁም የምርጫው ሂደት ፍትሐዊና ዲሞክራሲያዊ እንዲሆን የሽግግር መንግሥት ጥረት ማድረጉን ፣ በመሆኑም የምርጫው ሂደት ነፃና ዲሞክራሲያዊ በሆነ መልክ ለመምረጥ ያስችላሉ የተባሉ ሰዎች ተመርጠው የምርጫ ቦርድ መቋቋሙንና ቦርዱም የተቻለውን ያህል እንቅስቃሴ ማድረጉን ፣ በምርጫው የታየ ደካማ ጎን በአገራችን ያሉ ተቃዋሚዎች በሰፊት ያልተሳተፉበት መሆኑን ፣ ሆኖም የምርጫ ዲሞክራሲያዊነት የሚለካው በችግሮች መከሰት ወይም አለመከሰት ሳይሆን የሚከሰቱ ችግሮችን ለመፍታት የሚያስችል አሠራር በመኖሩ እንደሆነ ፣ ከዚህ አንፃር ተቃዋሚዎች ያልተሳተፉበት የጥምር ፓርቲ ሂደትን በአለመደገፍ አኩርፈው በመውጣትና ሸንፈትም ቢሆን የሕዝቡን ውሳኔ በፀጋ ባለመቀበል እንጂ ነፃና ዲሞክራሲያዊ በሆነ መንገድ በምርጫው ለመሳተፍ ታግደው እንዳልሆነ ፣ ዲሞክራሲያዊ በሆነ መንገድ በምርጫው ለመሳተፍ ታግደው እንዳልሆነ ፣ በምርጫው ወቅት ችግሮች ቢከሰቱም የምርጫ ቦርድ አስፈላጊውን እርምጃ ለመውሰድ የሚችልበት አሠራር እንደነበረና ከድርጅቶች ይልቅ በግል የተወዳደሩ በርካታ መሆናቸውን በሁለቱም በኩል ተሳትፎ እንደነበር አመልክተዋል ::



በተጨማሪም ለመምረጥ ከተመዘገበው ሕዝብ ውስጥ 87% በላይ እንዲሁም ሊመርጥ ከሚገባው ውስጥ ቢያስ ከ50 % በላይ መሳተፉ አመርቂ የሕዝብ ተሳትፎ እንደሆነና ምንም እንኳን ለብዙ ዓመታት የፀረ-ዲሞክራሲያዊ አሠራር የነበረበት አገር ቢሆንም ከሌሎች ብዙ አገሮች የተሻለ የሕዝብ ተሳትፎ መኖሩ እንደሚያሳይ የሕገ መንግሥት ጉባኤ አባላትም በሰፊው ሕዝብ ተሳትፎ ተወክለው መምጣታቸውን ስለሚያውቁ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ የሕዝብን ማኩረፍና በምርጫው አለመሳተፍ በማንሳት የቀበሌ ሊቀመንበር ከሚስቱና ከልጆቹ ጋር ወጥቶ ቢመርጥ የሕዝቡን መሳተፍ እንደማያሳይ የጠቆሙት በወከላቸው ሕዝብ ላይ መሳለቅ መሆኑን ጠቅሰዋል ::

በመቀጠልም ከክልል 14 የተወከሉት አቶ አብዱራዛቅ መሐመድ ባቀረቡት ሀሳብ ሕገ መንግሥቱ የረቀቀበት ሂደት ሲታይ በዲሞክራሲያዊ ሥርዓት ውስጥ ሊቀርቡ ይችላሉ የሚባሉ አማራጮችን በማካተት ለሕዝቡ የቀረቡለት ሕዝቡ ጥቅሜን ያስከብሩልኛል እንዲሁም እስከ አሁን ድረስ ያካሄድኩትን ትግል ያራምዱልኛል የሚለውን አማራጭ ሀሳብ እንዲመጥር መደረጉንና ረቂቅ ሕገ መንግሥቱ እንደገና ለሕዝቡ ቀርቦ እንደነበረ ፣ በመጨረሻም ለተወካዮች ምክር ቤት ቀርቦ አንድ ቀን ብቻ ሳይሆን ከሦስት ሳምንታት በላይ በሰፊው እንደተወያየበት ፣ ይህም ሂደቱን የተከታተሉ የሕገ መንግሥት ጉባኤ አባላትና በጉባኤው ላይ በታዛቢነት የተገኙ የተወካዮች ምክር ቤት አባላት እንደሚያስታውሱት በተጨማሪም አማራጭ ዕንስ ሐሳቦች እንዲቀርቡ ለማድረግ በተቻለ መጠን በሽግግር ዘመን ወቅት በሰላማዊ መልክ ትግል የሚያደርጉ የፖለቲካ ድርጅቶችና የብዙሃን ማህበራትን አካትቶ መሄዱ የአሠራሩን ሚዛናዊነት እንደሚያሳይ ፣ በመሆኑም ሕገ መንግሥቱ በሕዝብ ተወካዮች ሊፀድቅ የቀረበ ሰነድ መሆኑን አመልክተዋል ::

እያይዘውም ሰነዶቹ ሲታሸጉም ሆነ ሲከፈቱ የተወዳዳሪዎች ተወካዮች ተገኝተው የማረጋገጥና ድምፁን የመስጠት መብታቸው በመጠቀም ሲፈርሙበት እንደሆነና ይህም መከናወኑን በታዛቢዎች አማካይነት በየንዑስ ጣቢያዎች መረጋገጡን ጠቁመዋል ::

በተጨማሪም በምርጫው ለመወዳደር ዕድሜው የሚፈቅድለት ፣ ጤነኛ አእምሮ ያለው ፣ የመወዳደር መብቱን ያለተገፈፈና በሚወዳደርበት አካባቢ ቢያንስ ሁለት ዓመት የኖረ ለመወዳደር እንዳልተከለከለ ፣ የሚፈለገውን ያህል ተቃዋሚ

ኃይሎች ገብተው አስተዋፅኦ ሊያደርጉ የሚችሉበት ሁኔታ ቢኖርም ታግለው ለማታገል ባለመቻላቸው ከተቃዋሚዎች ጋር የተካሄደው ውድድር የቀዘቀዘ መሆኑን

ሆኖም በውድድሩ ወቅት 900 ያህል የግልና 500 ያህል የድርጅት ተወዳዳሪዎች ቀርበው እንደተስተናገዱ ፣ እያንዳንዱ ዕጩ ለውድድር በፈለገበት አካባቢ በነፃ በመንቀሳቀስ ዓላማውን ለማስገንዘብ የሞከረበት የተሟሟቀ ውድድር እንደነበረ ፣ እንዲሁም በሕገ መንግሥት ጉባኤ መክፈቻ ወቅት በኢትዮጵያ ብሔራዊ ምርጫ ቦርድ ሰብሳቢ እንደተጠቀሰው ክስ የቀረተበባቸው ጣቢያዎች በአግባቡ ተመርምረው አፋጣኝ ምላሽ እንዳገኙ ፣ አላግባብ የከሰሱትም አግባብ አለመሆኑን እንደተገለጸላቸው ፣ በልዩ ልዩ እክሎች ምክንያት ምርጫው የዘገየባቸው ደግሞ ሁሉም የኢትዮጵያ ሕዝቦች የወደፊት ዕድል በሚወሰንበት ሕገ መንግሥት ጉባኤ እንዲሳተፉ ሲባል የጊዜ መራዘም መደረጉን ፣ ስለዚህ በልዩ ልዩ ታዛቢዎች የተገለጸውና በጉባኤውም አባላት ላይ ከሚንጸባረቁ የተለያዩ አመለካከቶችም በመነሳት ምርጫው ዲሞክራሲያዊ መሆኑን ለመመልከት እንደሚቻል አስታውቀዋል ::

ከዚያም አቶ አሊ አብዶ ከክልል 14 ባቀረቡት ሀሳብ በክልል 14 በግል ከተመረጡት የጉባኤው አባላት ውስጥ የሕገ መንግሥቱን መዋቅርና የምርጫው ሂደት ዲሞክራሲያዊ እንዳልነበረ የጠቀሱት ሁለት አባላት መልሰው ሀሳባቸውን እንዲመለከቱ በማሳሰብ የየቀቤሌዎቹ ነዋሪዎች ቁጥር የተለያየ ሲሆን ሕዝቡ የተለያዩ አገሮችን ልምዶች በማገናዘብ ከሦስት በማያንሱ ተከታታይ ዕሁዶች ሀሳቡን እንደገለጸና በኋላም ለተወካዮች ምክር ቤት ቀርቦ በሰፊው ውይይት እንደተካሄደበት ከዚያም መሠረታዊ በሆኑ ጉዳዮች ላይ ሕዝቡ በአንድ ቀን ውስጥ ሀሳቡን መግለጹንና በዚያም ወቅት አወያዮች እንደነበሩት ፣ እንዲሁም ከክልል 14 ሁለት የፖለቲካ ድርጅቶችና ሌሎች የግል ተወካዮች በጉባኤው መገኘታቸው ሲታይ ሕገ መንግሥቱን የማርቀቅ ሂደት ዲሞክራሲያዊ መሆኑን እንደሚያረጋግጥና ለጉባኤው አባላት ምርጫው የተማረው የኅብረተሰብ ክፍል ብቻ ሳይሆን ጉባኤውን የሚወክለው ሁሉም ሕዝብ መሳተፉንና በሻለቃ አድማሴ ዘለቀንም ተፅዕኖ በሌለበት ሂደት ፍላጎታቸውን የሚያፀባርቁ በሺህዎች የሚቆጠሩ እንደመረጧቸው አመልክተዋል ::

በማስከተልም አቶ ጡቻ ኡቃ ከደቡብ ሕዝቦች ክልል በኃይለ ሥላሴና በደርግ ዘመን የነበረው ህገ መንግሥት ዲሞክራሲያዊ እንዳልነበረና ሕዝቡም ለ17 ዓመት እንደታገለ አስታውሰው የአሁኑ ሕግ መንግሥት ግን ከፅንሰ ሐሳቡ ጀምሮ ግለሰቦች ምሁራንና የፖለቲካ ድርጅቶች ተወካዮች የተሳተፉበት ፣ የተወካዮች ምክር ቤት በሰፊው የተወያየበትና ለሕዝቡ ሁለት ጊዜ ቀርቦ የሚፈልገውን ሀሳብ እንዲካተትበት





መደረጉን ፣ ሕዝቡም ስሜቱን ለመጠበቅ የተሻለውን መርጦ መላኩን ረቂቅ ሕገ መንግሥቱን ለመሻርም ሆነ ለማፅደቅ የሚችል አካል መሰየሙ ፣ በምርጫውም

ወቅት ተፅዕኖ ተደርጎብኛል የሚል የጉባኤው አባል መገኘቱ የምርጫው ዲሞክራሲያዊነት እንደሚያሳይ ገልጸዋል ::

ጉባኤው የ15ደ ደቂቃ ዕረፍት ካደረገ በኋላ ጊዜያዊ ሊቀመንበሩ እስከ አሁን ከሁለት የሕገ መንግሥት ጉባኤ አባላት በስተቀር የሕገ መንግሥት ማርቀቅ ሂደቱና የሕገ መንግሥቱ አፅዳቂዎች ምርጫ ዲሞክራሲያዊ ነበር የሚለው ሀሳብ በብዙ ሀሳቦች በመደገፉ ሂደቱ ዲሞክራሲያዊ አልነበረም የሚል ሀሳብ እንዲቀርብ ጠይቀው አንድ የክልል 5 ተወካይ በጉባኤው ውስጥ ብዙ የእስልምና ሃይማኖት ተከታዮች በመኖራቸው የመስገጃ ሰዓት በመድረሱ የሻይ ዕረፍቱ ገፋ ብሎ ጊዜ እንዲሰጣቸው ጠይቀው ጥያቄው ትክክለኛ መሆኑንና ከሚቀጥለው ቀን ጀምሮ ተግባራዊ የሚሆን መሆኑን ለዛሬ ግን ይቅርታ በመጠየቅ ጊዜያዊ ሰብሳቢው ጉባኤው ውይይቱን እንዲቀጥል አሳሰበዋል ::

በመቀጠልም አቶ ዳንኤል በላይነህ ከክልል 14 የሕገ መንግሥቱ አፅዳቂዎች ምርጫን አስመልክቶ በውጭ ሀገር ያሉትን ተቃዋሚዎች ሆነ የደርግ ኢሠፓ አባላትን እንኳን ቢሆን ከስህተታቸው በሚማሩበት መንገድ ተቀስቅሰው በምርጫው ባለመሳተፋቸው ምርጫው ዲሞክራሲያዊ አልነበረም የሚል አቋም እንዳላቸው ተናግረዋል ::

በማስከተልም ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 የአቶ ዳንኤል በላይነህን ሀሳብ በመደገፍ ማንኛውም ሰው በፈጸመው ወንጀል በግሉ መቅጣት እንጂ በጥቅሉ ወደው ሳይሆን ተገደው በወንጀለኛ ድርጅት የታቀፉትን ነገር ግን ከወንጀል ነፃ የሆኑትን ንፁሐን ዜጎች ስለሚጎዳ እንዲህ ዓይነቱ ድርጊት የሰብአዊ መብቶችን ቻርተር ስለሚቃወም የተካሄደው ምርጫ ዲሞክራሲያዊ አልነበረም የሚል አቋም እንዳላቸው ገልጸዋል ::

ከዚያም ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ከክልል 5 በጉዳዩ ላይ በቂ ሀሳብ ስለተሰጠበት ወደ ውሳኔ እንዲኬድ ባሳሰቡት መሠረት ጉባኤው ውይይቱን አቁሞ ወደ ውሳኔ እንዲሄድ ወይም እንቀጥል በሚሉት ሀሳቦች ላይ ድምፅ ተሰጥቶ ወደ ውሳኔ እንሂድ የሚለው ሀሳብ በአብዛኛው የጉባኤው አባላት በመደገፉ ጉባኤው ወደ ድምፅ መስጠት አምርቷል ::

በዚሁ መሠረትም የሕገ መንግሥት ማርቀቅ እና የአፅዳቂዎች ምርጫ ሂደት ዲሞክራሲያዊ ነበር የሚለው 520 የጉባኤው አባላት ፣ ሂደቱ ዲሞክራሲያዊ አልነበረም የሚለው በ2 የጉባኤው አባላት ሲደገፍ ፣ 5 የጉባኤው አባላት ደግሞ ድምፀ ተአቅቦ አድርገዋል :: በተሰጠው ድምፅ መሠረትም ጥቂት ድምፅ ያልሰጡ

አባላት ቢኖሩም ጉባኤው የሕገ መንግሥቱ የማርቀቅና የሕገ መንግሥት አፅዳቂዎች ምርጫ ሂደት ዲሞክራሲያዊ እንደነበረ ወስኖ አልፏል ።

ጉባኤው ቀጥሎ የተመለከተው አጀንዳ የጉባኤውን አመራር አባላት የሚያስመርጥ አስመራጭ ኮሚቴ መምረጥ ሲሆን የጊዜያዊ ኮሚቴው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ ለአስመራጭ ኮሚቴው ሰባት አባላት በዕጩነት ተጠቁመው አምስት አባላት የሚመረጡበትን ሀሳብ ኮሚቴውን በመወከል አቅርበው ቤቱ በአባለቱ ቁጥር ላይ ሀሳብ ካለው ሊያቀርብ እንደሚችል ገልጸዋል ።

በዚህም መሠረት ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 ጉባኤው ከተለያዩ ፓርቲዎችና ብሔር/ ብሔረሰቦች ተመርጦ የመጣ በመሆኑ በጥቆማና በድምፅ ከተመረጠ በአንድ ፓርቲ ሊያዝ ስለሚችል ዲሞክራሲያዊነቱን ለመጠበቅ የአስመራጮችም ሆነ የተመረጮች ተዋጽኦ ከተለያዩ ፓርቲዎች እና ብሔር/ብሔረሰቦች እንዲሆን ሀሳብ አቅርበዋል ።

ጊዜያዊ ሰብሳቢው በጉባኤው የሚገኙ አባላት የመምረጥም ሆነ የመመረጥ መብት ስላላቸው ጉባኤውን የሚመሩትንም ሆነ አስመራጮቹን ለምርጫ አቅርቦ ድምፅ ሰጥቶ የሚመረጡበትን አሠራር ጉባኤው እንደሚከተልና ከዚህ የተለየ አሠራር ሊኖር እንደማይችል አስታውቀዋል ።

በሌላ በኩል አቶ ሁሴን መሐመድ ከክልል 4 ጊዜያዊ ኮሚቴው እስከ አሁን ድረስ ተገቢውን አመራር እየሰጠ በመሆኑ የኘው ኮሚቴ የአመራር አባላቱን እንዲያስመርጥ ሀሳብ አቅርበው የተለያዩ ሀሳቦች የተወከሉበት ጉባኤ በመሆኑ ለጊዜው ጉባኤውን የሚመሩት 3 አባላት በቂ እንዳልሆኑና የአመራር አባላቱን ለመምረጥ ሰፋ ማለት እንደሚገባው ደ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ከአሳሰቡ በኋላ ከቤቱ 5 ሰዎች በዕጩነት ተጠቁመው 3 ሰዎች ለአስመራጭነት ይመረጡ የሚል ሀሳብ ቀርቧል ።

በመቀጠልም አቶ አባይ ፀሐይ ከክልል 1 ለአስመራጭ ኮሚቴነት 5 ሰዎች በቂ ናቸው የሚል ሀሳብ እንዳላቸው ገልፀው ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ደጋግመው ያነሱት በግልፅ ተመልሶላቸው እንዲሄድ ማስፈለጉን ጠቁመው ማየት የሚገባው ለጉባኤው የተመረጡ አባላት ምን ያህል ነፃና ዲሞክራሲያዊ በሆነ መንገድ

ተመርጡ የሚለውን እንጂ ሁለቱም ፆታዎች ከተለያዩ ሃይማኖቶችና ብሔር/ብሔረሰቦች እንዲሁም ከ30 በላይ ፓርቲዎች በተወከሉበት ጉባኤ ሁሉንም መወከል እንደማይቻል ሁሉም የግድ መወከል አለባቸው የሚለው ሀሳብ ምን ያህል ዲሞክራሲያዊ እንደሆነ ጠይቀው ሕዝቡ የወከለው ግለሰብ ሀሳቡን በትክክል ካላንፀባረቀ ተወካዩ መቀየር ስለሚችል ችግር እንደሌለበትና ሌላ ሀሳብ ካላቸው በግል እንዲያስቀምጡ አሳስበዋል ።





በዚህ ላይ መወሰን የሚገባው የአስመራጭ ኮሚቴው አባላት ቁጥር ብቻ ሳይሆን ተዋፅኦም እንደሆነ ፣ የክልል ምክር ቤት አባላት ምርጫ እስከ አሁን የብሔር ተዋፅኦ እየተጠበቀ ሲመረጥ እንደቆየ ለአስመራጭ ኮሚቴ አባላት ምርጫም በዚሁ

መልክ እንዲሆን ሀሳብ ቀርቦ በጉባኤው የተወከሉ አባላት የመምረጥና የመመረጥ መብት ያላቸው መሆኑን የጉባኤው አባላት የሕዝብ ተወካዮች እንጂ የድርጅት ተወካዮች አለመሆናቸውን ነገር ግን ድምፅ በሚሰጥበት ጊዜ በድርጅት ወይም በብሔር/ብሔረሰብ ሊሆን እንደሚችልና ይህንንም የድምፅ ውጤት እንደሚያስታውቅ ጊዜያዊ ሰብሳቢው አስረድተዋል ።

በመጨረሻም አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 በጉባኤው የተወከሉ ተወካዮች የተለያዩ ብሔር/ብሔረሰቦችና ሕዝቦች ወክለው የመጡ መሆናቸውንና በተቻለ መጠን የሚመረጡት የተለያዩ ኮሚቴዎች አባላት ምርጫ ሁኔታ በፈቀደ መጠን የተለያዩ ሕዝቦችን ውክልና እና ተሳትፎ እየታየ መፈጸም እንደሚገባውና ይህም ዋነኛ መርሆ መሆን እንደሚገባና በተለያዩ የአመራር ቦታዎች የተለያዩ ሕዝቦች ፍትሐዊ የሆነ ውክልና ማግኘት እንደሚገባቸው ጠቁመው በጉባኤው ላይ ኢሕአዴግ ከ85% በላይ መቀመጫዎች ስላሉት ሁሉንም የአመራር ቦታ ጠቅልሎ መያዝ አለብኝ የሚል ዕምነት እንደሌለው ፣ ኢሕአዴግ ከማይንቀሳቀስባቸው ክልሎች የተወከሉ የጉባኤ አባላት የጉባኤውን ሂደት የማሳካትና የሀገሪቱን የበላይ ሕግ የማፅደቅ ከፍተኛ ኃላፊነት ስላላባቸው እና የሕዝብ ተወካዮች መሆናቸውን እና በአመራር ኃላፊነት ቦታ እንዲሰጣቸው ኢሕአዴግ እንደሚያምን ገልፀዋል ።

ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ የጊዜያዊ ኮሚቴው ሰብሳቢ በጉባኤው ውስጥ ከተለያዩ ድርጅቶ የተመረጡ አባላት ያሉ በመሆኑ የተለያየ ሀሳብ እንዳለቸው እንደሚያምኑና ጉባኤው ወደኮሚቴዎች በሚያመራበት ጊዜ የሚመርጠውን ሰው የመወሰን መብት እንዳለው በግልጽ የተቀመጠ በመሆኑ ለአስመራጭ ኮሚቴ አባልነት 3 ፣ 5 ፣ 7 ይመረጡ የሚል ሀሳብ በመቅረቡ አንዱን በድምፅ መርጦ ወደአስመራጭ ኮሚቴ ምርጫ እንዲሄድ ማሳሰቢያ አቅርበዋል ። በዚህ ጊዜ 3 አባላት ይመረጡ የሚለው ሀሳብ ያቀረቡት የጉባኤው አባል ሀሳባቸውን በማንሳታቸው ጉባኤው 5 ወይም 7 አባላት ይመረጡ በሚሉት ድምፅ ሰጥቷል ። በዚህም መሠረት 6 አባላት ለአስመራጭ ኮሚቴ አባልነት 7 አባላት ይበቃሉ ሲሉ፣ 478 አባላት ደግሞ 5 አባላት ይበቃሉ በማለታቸውና 2 ድምፀ ተአቅቦ በመመዝገቡ የጉባኤው አስመራጭ ኮሚቴ ቁጥር 5 እንዲሆን ጉባኤው ወስኗል ።

በውሳኔው መሠረት 5 የአስመራጭ ኮሚቴ አባላትን ለመምረጥ 7 አባላት በዕጩነት እንደሚከተው ጥቆማው ተካሂዷል ፣

1. አቶ ገዝሙ ቀልቦ ከደበቡብ ሕዝቦች ክልል
2. አቶ አሊ አብዶ ከክልል 14
3. ኢ/ር አብያሌ ፍላቴ ከክልል 6
4. ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ከክልል 5
5. አቶ ኃይሉ ገመዳ ከክልል 4
6. ወ/ሮ ፅጌ አስፋው ከክልል 3
7. አቶ ሽዊት ገብርስቶስ ከክልል 1

የጉባኤው 1/3ኛ ድምፅ በማግኘት በዕጩነት የተመረጡት በድምፅ መሠረት ፣

| | |
|---|---|
| 1. ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ከክልል 5 | 463 ድምፅ |
| 2. አቶ ገዝሙ ቀልቦ ከደቡብ ክልል | 422 ድምፅ |
| 3. ወ/ሮ ፅጌ አስፋው ከክልል 3 | 416 ድምፅ |
| 4. አቶ አሊ አብዶ ከክልል 14 | 410 ድምፅ |
| 5. ኢ/ር አብያለ ፍላቴ ከክልል 6 | 280 ድምፅ |

በማግኘት ለጉባኤው አመራር አባላት አስመራጭ ኮሚቴ አባልነት ሲመረጡ

| | |
|---|---|
| 1. አቶ ሽዊት ገብርስቶስ ከክልል 1 | 254 ድምፅ |
| 2. አቶ ኃይሉ ገመዳ ከክልል 4 | 165 ድምፅ |

በማግኘታቸው ሳይመረጡ ቀርተዋል ፡፡

በመጨረሻም የጊዜያዊ ኮሚቴው ሰብሳቢ የተመረጠው አስመራጭ ኮሚቴ የሥራ ክፍፍል አድርጎ እንዲያድር አሳስበው ጉባኤው ለሚቀተለው ቀን 3 ሰዓት ተቀጥሮ ስብሰባው ከምሽቱ 1፡15 ሰዓት ተጠናቋል ፡፡



የኢትዮጵያ ሕገ መንግሥት ጉባኤ ጥቅምት 19 ቀን 1987 ዓ.ም የቀጠለ ሲሆን በቅድሚያ የአስመራጭ ኮሚቴው አባላትን ለመምረጥ ቀደም ሲል የተቋቋመው ጊዜያዊ ኮሚቴ ሰብሳቢ ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ከክልል 4 የዕለቱ አጀንዳ የጉባኤውን አመራር ኮሚቴ አባላት መምረጥ እንደሆነ አሳስበው የአስመራጭ ኮሚቴ አባላት ቦታቸውን እንዲይዙ ጠይቀዋል ፡፡

በዚህም መሠረት የአስመራጭ ኮሚቴው አባላት መድረኩን የተረከቡ ሲሆን ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ከክልል 5 በሰብሳቢነት መርጠዋል ፡፡

ሊቀመንበሩ የሕገ መንግሥቱ ጉባኤ የሚመራ ኮሚቴ አባላት 3 ቢሆኑ እንደሚሻልና አመራረጣቸውም በቅድሚያ 5 ሰዎች ከተጠቆሙ በኋላ በሚስጥራዊ ድምፅ አሰጣጥ ሥርዓት እንደሚሆን ገልጸው ከተመረጡት 3 ሰዎች መካከል ሊቀመንበሩ ፣ ፀሐፊውና ምክትል ፀሐፊው ራሳቸው እንዲመርጡ ቢደረግ በሚለው ላይ የቤቱን ሀሳብ ጠይቀዋል ፡፡

አያይዘውም ወደ ጥቆማው ከመግባቱ በፊት በቅድሚያ በዕጩነት የሚቀርቡት አባላት ብዛት መወሰን እንደሚገባው አቶ አዲሱ ለገሠ ከክልል 3 በማሳሰባቸው ይህንኑ ሁሳብ ቤቱ እንዲወስንበት ሰብሳቢው አሳስበዋል ፡፡

አቶ አዳሙ ደገፋው ከክልል 14 ደግሞ ምንም እንኳን እያንዳንዱ የጉባኤ አባል የሕዝብ ተወካይ ቢሆንም በምርጫው ጊዜ ግን ከፍተኛ ድምፅ ያለው ኢሕአዴግ ብቻ አሸናፊ በመሆን የሌሎች ድርጅቶችና ግለሰቦች ውክልና እንዳይኖር ያደርጋል የሚል ሥጋት እንዳላቸው ገልጸዋል ፡፡

ይህንኑ በተመለከተም የአስመራጭ ኮሚቴው ሰብሳቢ በዲሞክራሲያዊ ፓርላሜንታሪ አሠራር ሁሉጊዜ ተቀባይ የሚሆነው አብዛኛውን የድምፅ ድጋፍ የሚያገኝ ሀሳብ ብቻ ሳይሆን አንስተኛ ድምፅ የሚስተናገድበት ሁኔታ እንዳለ ይህ አሠራርም የሕገ መንግሥት ጉባኤ የሚከተለው ስለሚሆን ሰፋ ያለ የሕዝብ ውክልና ያለው ድርጅት ሀሳብ ብቻ ይራመዳል ማለት እንደማያስኪድ ፣ ኮሚቴዎች በሚዋቀሩበት ጊዜም በአመራሩ ውስጥ ዕድል ያላገኙ አንስተኛ ወገኖች የመካተት ዕድል እንደሚኖራቸው ገልጸው በቅድሚያ ግን ዕጩዎች ስንት ይሁን የሚለው ጉባኤው እንዲወሳን አሳስበዋል ፡፡

በዚህም መሠረት ለጉባኤው አመራር አባላት 5 ዕጩዎች ተጠቁመው 3 እንዲመረጡ ሀሳብ የቀረበ ሲሆን አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 115 ዕጩዎች ተጠቁመው 3 ይመረጡ የሚለውን ሀሳብ እንደሚደግፉ ገልጸው ከዚህ በተጨማሪ ግን በሕገ መንግሥቱ ሰነድ ላይ ውይይት ሲካሄድ የሚቋቋሙት ኮሚቴዎች አመራር አባላት አሁኑኑ ቢመረጡ እንደሚጠቅምና የኮሚቴዎች ቁጥርና የአባላት ብዛት ግን የሕገ መንግሥቱን ሰነድ አፊሴላዊ በሆነ መልኩ ጉባኤው ከተረከበ በኋላ የሚወሰን እንደሆነ ጠቅሰዋል ::

ሰብሳቢው በበኩላቸው በቅድሚያ የአመራር ዕጩዎች መጠቆምና መምረጥና የኮሚቴዎችን በተመለከተ ግን ቀጥሎ ቢታይ እንደሚሻል አሳስበዋል ::

አቶ ታደሰ ካሳ ከክልል 3 በሰጡት አስተያየት በቅድሚያ 3 የአመራር አባላት እንዲመረጡና ከመካከላቸው ሊቀመንበር ፣ ፀሐፊና ምክትል ፀሐፊ የሚሆነው ደግሞ በኋላ ቢወሰን ይሻላል የሚል ሀሳብ አቅርበዋል ::

ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 ደግሞ በዲሞክራሲያዊ ፓርላሜንታሪ አሠራር የአወያይ ኮሚቴ አባላት የሥራ ድርሻ ሀሳብ ከቤቱ በሚሰነዘርበት ጊዜ ለድምፅ አቅርቦ ማስወሰን እንጂ ይኸኛው አጀንዳ ከዚያኛው መቅድም አለበት የሚል ብይን የመስጠት መብት እንደሌለ ፣ በዚህ ረገድ በአስመራጭ ኮሚቴው በኩል በቅድሚያ የአመራር አባላት ይመረጡ ተብሎ የቀረበው ሀሳብን የማትረብ መብት የሚገድብ ዲሞክራሲያዊ አሠራርን ያልተከተለ አካሄድ እንደሆነ ገልጸው በድምፅ ብቻ የሚወሰነው ውሳኔ 80% በላይ የጉባኤ አባላትን ያካተተው ኢሕአዴግ ብቻ የሚጠቀምበት እንደሚሆን አመልክተዋል ::

ለዚህም ሰብሳቢው በሰጡት ምላሽ በቅድሚያ ተቆማና ምርጫ ይካሄድ በሚል ከአስመራጭ ኮሚቴው የተሰጠው አስተያየት የአካሄድ ኢንፎርሜሽን እንጂ ብይን እንዳልሆነ ፣ የሚቀርብ ሀሳብንም ለመግታት እንዳልተሞከረ ፣ ኢንፎርሜሽን መስጠት ደግሞ የፓርላሜንታሪ አሠራር የሚፈቅደው እንደሆነ ዕውቅ መሆኑን ገልጸው ማንም የጉባኤ አባል ሀሳቡን የመግለጽ መብቱ ማንም እንደማይገድበውና ኢሕአዴግ ሰፊ ውክልና ያለው ስለሆነ የሚያራምደውን አመለካከት በጭፍን መቀበል ይኖራል ማለት እንደማይቻል አስታውቀዋል ::

ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ከክልል 4 በበኩላቸው የሚጠቆሙት ዕጩዎች ስማቸውና ማንነታቸው ስለሚገለጽ የሚፈልጉትን ሰው ለይቶ ለመምረጥ እንደሚቻል ፣ አስመራጭ



ኮሚቴው ሲመረጥ እንደታየውም ኢሕአዴግ ከፍተኛ ውክልና ስላለው ብቻውን ይመረጣል የሚለው ትክክል አለመሆኑን እንደሚያረጋግጥ አመልክተዋል ::

ከዚያም የዕጩዎች ጥቆማ ተካሂዶ ፣

| | | |
|---|---|---|
| 1. አቶ አባተ ኪሾ | ከደቡብ ሕዝቦች ክልል | |
| 2. ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ | ከክልል | 4 |
| 3. አቶ አዲሱ ለገሠ | ከክልል | 3 |
| 4. አቶ ዑመር አብዱሠታር | ከክልል | 13 |
| 5. አቶ ዮሱፍ መሐመድ | ከክልል | 2 |

በዕጩነት ተጠቁመዋል ::

በመቀጠልም ሰብሳቢው የሚስጥር ድምፅ መስጫ ካርድ ታትሞ እስከሚመጣ ድረስ ከቀረቡት ዕጩዎች ተመርጠው አመራሩን ከሚይዙት ሰዎች መካከል ሊቀመንበር ፣ ፀሐፊና ምክትል ፀሐፊ የሚሆነው ራሳቸው በሚያደርጉት ውሳኔ ወይስ በሚመረጡበት ጊዜ ከፍተኛውን ድምፅ ያገኘው ሊቀመንበር ፣ በሁለተኛ ደረጃ ከፍተኛውን ድምፅ ያገኘው ፀሐፊ ፣ ሦስተኛውን ከፍተኛውን ድምፅ ያገኘው ምክትል ፀሐፊ በሚለው ላይ ሀሳብ እንዲሰጥበት ሀሳብ አቅርበዋል ::

በዚህም መሠረት ጉባኤው መብቱን ተጠቅሞ የአመራር አካላቱን ከመረጣቸው በኋላ ሊቀመንበሩን ፣ ፀሐፊውንና ምክትል ፀሐፊውን ራሳቸው ተመካክረው ቢወስኑ ችግር እንደሌለው በአቶ ታደሰ ካሳ ከክልል 3 እና በአቶ ዮሴፍ በራሳ ከደቡብ ሕዝቦች ክልል አስተያየት ቀርቧል ::

በሌላ ኩል ደግሞ ዕጩዎች ሲመረጡ የሚያገኙት ድምፅ በአመራር የሚኖራቸውን ድርሻ መወሰን ስለሚገባውና የጉባኤውን ሂደት ለሚከታተለው ሕዝብም ተገቢ ሆኖ የሚገኘው ይኸው አሠራር ስለሆነ እንዳገኙት ድምፅ ቅድም ተከተል ሊቀመንበር ፣ ፀሐፊ እና ምክትል ፀሐፊ መሆን እንደሚሻል ከክልል 14 አቶ ዘለሌ ፀጋሥላሴ እና አቶ መኩሪያ ታፈሰ ሀሳብ አቅርበዋል ::

አቶ አባይ ፀሐዬ ከክልል 1 ደግሞ በቅድሚያ ምርጫው ቢካሄድ እንደሚሻል አሳስበው የአመራሮችን የሥራ ድርሻ አሰያየም ግን ራሳቸው ተመራጮቹ ይወስኑ ወይም እንዳገኙት ድምፅ ቅድም ተከተል ይሰየሙ የሚለው ሁኔታ በኋላ ቢወሰን የቀረቡትን አስተያየቶች ለማስተረቅ እንደሚረዳ ገልጸዋል ::

አቶ ዘለሌ ፀጋሥላሴም የአቶ አባይ ፀሐዬ ያቀረቡትን ሀሳብ እንደሚቀበሉትና የአመራር አካላት በምርጫ መመዘኛ ከሁሉም በላይ ብቃት መሆን እንደሚገባው ጠቅሰዋል ::

የአስመራጭ ኮሚቴው ሰብሳቢ በበኩላቸው አቶ አባይ ፀሐዬ ያቀረቡት ሀሳብ አስታራቂነት ገልጸው የኮሚቴው አመራር አካላትንም ይጨምር በሚል የተሰነዘረው ሀሳብ ተብራርቶ እንዲቀርብና ካርዱ እስኪዘጋጅ ድረስ ውይይት እንዲካሄድ ጠይቀዋል።

በዚህም መሠረት አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ በሰጡት ማብራሪያ የሕገ መንግሥት ጉባኤ አባላት የተለያዩ የኅብረተሰብ ክፍሎች ተወካዮች ከመሆናቸው አንፃር 3 አመራር አካላት ቢመረጡ የሚያጡትን የአመራር ውክልና ለማካካስ እንዲቻል ሚዛናዊ በሆነ መልኩ የጉባኤ አባላት አመራር እንዲያገኙ የኮሚቴ አመራር አባላትንም አብሮ መመረጥ እንደሚሻል ገልጸው ፣ ስለኮሚቴዎች ምንነትና ብዛት ግን ከሰነዱ ርክክብ በፊት መናገር እንደማይቻል ጠቅሰዋል ።

አቶ ሸምሰዲን አህመድ ከክልል 5 በአመራሩ ውስጥ የውክልና ስብጥር እንደሚደግፉ ገልጸዋል ።

አቶ ደረጀ ዱኬሳ ከደቡብ ሕዝቦች ክልል እና አቶ ታደሰ ካሳ ከክልል 3 ባቀረቡት ተመሳሳይ ሀሳብ ደግሞ ጉባኤው እንዲያከናውን የሚጠበቅበት በርካታ ተግባሮች ለማሳካት እንዲረዳ የሚቋቋሙት ኮሚቴዎች የአመራር አካላት የዋናው አመራር አባላት አካል መሆናቸውና አብረውም መመረጣቸው ተገቢ እንደሆነ ገልጸዋል ። ከክልል 4 አቶ አስፋው ቀኖም ጉባኤውን በ3 ሰዎች መምራት ስለሚከብድ የኮሚቴ አባላት አብረው መመረጣቸው እንደሚደገፍ ተናግረዋል ።

አቶ ግርማ ተሰማ ከክልል 14 በበኩላቸው የኮሚቴው አመራር አካላት አብረው ይመረጡ የሚለውን ሀሳብ የሚቃወም ስለሌለ በጉዳዩ ላይ የሚካሄደው ውይይት በዚሁ እንዲያበቃ ያሳሰቡ ሲሆን አቶ መሐሙድ ድሪር ከክልል 5 ደግሞ የቀረበውን ሀሳብ እንደሚደግፉትና ድምፅ ሲሰጥ ግን በአማርኛ ፊደል ጽፈው ድምፅ መስጠት የሚቸግራቸው የጉባኤ አባላት ሁኔታው እንዲመቻችላቸው አሳስበዋል ።

የአስመራጭ ኮሚቴው ሰብሳቢም በአማርኛ ፊደል መጠቀም የማይችሉ የጉባኤ አባላት ረዳት እንደሚመደብላቸው ጠቅሰው፣ የአመራር አባላት ውክልና ሚዛናዊና የኅብረተሰቡ ስብጥር ያለው እንዲሆንና የኮሚቴ አባላትም አብረው ይመረጡ በሚለው ላይ ቤቱ ስምምነት እንደሚታይ ገልጸዋል ።

አቶ ጀንበሬ ገ/መድህን ክልል 14 ደግሞ ዕጩ የአመራር አባላት የሕይወት ታሪካቸው ለጉባኤው እንዲናገሩ አሳሰቡ ፣ የምርጫ ካርዱ ተዘጋጅቶ እስከሚመጣ ድረስ ግን ራሳቸውን ማስተዋወቅ እንደሚያስፈልግ አመልክተው ጉባኤው ለሻይ ዕረፍት ተነስቷል ።



ከሻይ ዕረፍት በኋላም የጉባኤው አመራር ዕጩ አባላት ራሳቸውን ያስተዋወቁ ሲሆን የአስመራጭ ኮሚቴው ሰብሳቢም የምርጫ ካርዱ ተዘጋጅቶ እንዳልደረሰ አስታውቀዋል ።

ከዚያም አቶ ግርማ ብሩ ከክልል 4 ድምፅ ከተሰጠ በኋላ ስብሰባው እንደገና የሚጀመርበት ሰዓት እንዲወሰን አሳስበዋል ።

በዚህም መሠረት የአስመራጭ ኮሚቴው ሰብሳቢ ድምፅ ለመቁጠር ጊዜ ስለሚወስድና የፀሎት ጊዜ የሚፈልጉ አባላት ከመኖራቸው አንፃር ጉባኤው ከቀኑ 9 ሰዓት ቢጀመር እንደሚሻልና የውይይቱ አጀንዳም የአመራር አባላት የሥራ ድርሻ አሰያየምን በተመለከተ የቀረበው አማራጭ ሀሳብ እንዲሆን የገለጹ ሲሆን ፣ ቤቱም በዚሁ ተስማምቶ ከጧቱ በ5 ሰዓት ከ15 ደቂቃ በሚስጥር ድምፅ የመስጠቱ ሂደት ተጀምሯል ።

ከሰዓት በኋላ በቀጠለው ጉባኤም የአስመራጭ ኮሚቴው ጧት የተካሄደውን የጉባኤው ቋሚ አመራር አካላት ምርጫ ውጤትን በተመለከተ ሪፖርት አቅርቧል ።

በዚሁ መሠረትም ቋሚ የአመራር አካላቱን ለመምረጥ በድምሩ 522 የጉባኤ አባላት ድምፅ መስጠታቸውን ፣ ከእነዚህም ውስጥ አራቱ /4/ የዕጩዎች ስም በትክክል ወይም በግልጽ ያልተጻፈባቸው ሆነው በመገኘታቸው እንዳልተያዙ ተገልጿል ።

የአስመራጭ ኮሚቴው በትክክል ድምፅ የሰጡ ናቸው ብሎ ከተቀበላቸው 518 ድምጾች ውስጥ ፦

| | | |
|---|---|---|
| 1. ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ | ከክልል 4 | 504 ድምፅ |
| 2. አቶ አባተ ኪሾ | ከደቡብ ሕዝቦች ክልል | 491 ድምፅ |
| 3. አቶ አዲሱ ለገሠ | ከክልል 3 | 475 ድምፅ |
| 4. አቶ ዩሱፍ መሐመድ | ከክልል 2 | 26 ድምፅ |
| 5. አቶ ዑመር አብዱስታር | ከክልል 13 | 25 ድምፅ |

አግኝተዋል ።

በዚሁም መሠረት ከፍተኛ ድምፅ ያገኙት ሦስት ሰዎች ወደ መድረኩ እንዲመጡና የሥራ ክፍፍል እንዲያደርጉ የአስመራጭ ኮሚቴው ሰብሳቢ ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ባሳሰቡት መሠረት ተመራጮች ተወያይተው ፣

1. ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ የጉባኤው ሊቀመንበር
2. አቶ አዲሱ ለገሠ የጉባኤው ፀሐፊ
3. አቶ አባተ ኪሾ የጉባኤው ምክትል ፀሐፊ

ሆነው የሥራ ክፍፍል ማድረጋቸውን የአስመራጭ ኮሚቴው ሰብሳቢ ገልጸው ይህን የሥራ ድልድል ጉባኤው እንዲያጸድቀው በጠየቁት መሠረት ጉባኤው በሙሉ ድምፅ ያፀደቀው ሲሆን የጉባኤው ቋሚ አመራር አባላትም መድረኩን ተረክበዋል ።

የጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ባደረጉት ንግግር ጉባኤው እምነት ጥሎ እነሱን በመምረጡ አመስግነው በቤቱ ውስጥ የተለያዩ ሀሳቦች ፍትሐዊ በሆነ መንገድ እንዲሽራሸሩ ለማድረግ እንደሚጥሩ ቃል ገብተው ጉባኤውም ለሥራቸው መቃናት ከጎናቸው እንደሚቆም እምነታቸው መሆኑን ገልጸዋል ።

ከዚያም በሕዝብ አስተያየት የዳበሩትን የሕገ መንግሥት ጽንሰ ሐሳቦች መሠረት በማድርግ የሕገ መንግሥት ኮሚሽን ያረቀቀውን ሕገ መንግሥት ለተወካዮች ምክር ቤት አቅርቦት ምክር ቤቱ ለ12 ቀናት ሰፊ ውይይት አድርጎ ያሻሻለውን ረቂቅ የተወካዮች ምክር ቤት ምክትል ሊቀመንበር ዶ/ር ፈቃደ ገዳሙ ሲያስረክቡ የሚከተለውን ንግግር ካደረጉ ፣

ክቡር የሕገ መንግሥት ጉባኤ ሊቀመንበር !

ክቡራትና ክቡራን የሕገ መንግሥት ጉባኤ አባላት !

በዛሬው ታሪካዊ ቀን የሽግግሩ መንግሥት የተወካዮች ምክር ቤትን በመወከል የኢትዮጵያ ሕዝቦች ብሔሮችና ብሔረሰቦች የወከልዋቸው የሕገ መንግሥት ጉባኤ አባላት ፊት ቆሜ የሕገ መንግሥት ረቂቅ ለማስረከብ በመታደሌ ታላቅ ክብርና ልዩ ደስታ ይሰማኛል ።

የሚፀድቀው ሕገ መንግሥት የምንገነባቸው የዲሞክራሲ መዋቅር የማዕዘን ድንጋይ ለመሆን ስለሚችል የሁላችንም ተቀዳሚ ተግባር እንደሆነ መታወቅ አለበት ። ስለሆነም በተለያዩ የፖለቲካ ሀሳቦች ፣ ፖሊሲዎች ወይም ፓርቲዎች ብንለያይም የዲሞክራሲ መሠረት የሆነውን ሕገ መንግሥት እንዲኖረን ጥረት ማድረግ የጋራ ኃላፊነታችን ነው ። ይህ ካልሆነ ዲሞክራሲ ባልጎለበተበት ሁኔታ በምን መመዘኛና ሥርዓት የፖለቲካ ልዩነቶችን አንፀባርቆ በአማራጭነት የሚቀርቡት ፖሊሲዎች በሕዝብ አስመርጦ ተግባራዊ ለማድረግ ይቻላል ? ነገር ግን በሕገ መንግሥቱ በመንደርደር የዲሞክራሲን ሂደት አዳብሮ ወደ ተፈለገው ውጤት ለመድረስ ይቻላል ።

ይህ ሕገ ረቂቅ ሕገ መንግሥት በውስጡ ያካተታቸው ጽንሰ ሐሳቦች በሚከተለው አኳኋን የተገነቡ በመሆናቸው ዲሞክራሲያዊና ለችግሮቻችን ፍቱን ይዘት እንዳላቸው እምነት ሊያድርብን ይገባል ። እነዚህም ፣

- በተለያየ ደረጃ በሽግግሩ መንግሥት መዋቅሮችና በሕዝብ ውይይቶች የዳበሩ መሆናቸውን



- በዓለም ዲሞክራሲ ዕድገት ከተደረሰበት ደረጃ የተገናዘቡ ሀሳቦች በማዘሉ
- የአገራችን ልዩ የማህበራዊና የፖለቲካ ችግሮችን ሁኔታዎች አጢኖ መፍትሔዎችን ለማስገኘት የሚያስችል በመሆኑ ፣
- የተለያዩ የፖለቲካ ሀሳቦችን ያዘለ ፣ ማለትም በብዙሃንና በአናሳ ድምፅ የተደገፉትን አንቀጾች ስላካተተ ነው ።

ከሁሉም በላይ በሕገ መንግሥቱ ሊፀድቅ የቀረበው በኢትዮጵያ ሕዝብ ተወካዮች ስለሆነ፣ ዲሞክራሲያዊነቱ እሙን ያደርገዋል ።

ሕገ መንግሥቱ ለሚወጡ ሕጎች ሁሉ ምንጭ ከመሆኑም በላይ በአሁኑ ወቅት ለምንገነባው ሕይወታችን መሠረት እንደሚሆን አሌ አይባልም ። ዋና ዋናዎቹ ለመጠቀስ ፣ በትግልና በተከፈለው መስዋዕትነት የተገኘው ሰላምና እስከ አሁን የተገነባው ዲሞክራሲ ዘላቂ ለማድረግ ፣ አንድ ጠንካራ የኢኮኖሚና የፖለቲካ ማህበረሰብ ለመገንባትና ፍትሕ የሰፈነበት የሰብአዊ መብትና የብሔረሰቦች መብቶች የተረጋገጡበት ሥርዓት ለመዘርጋት ያስችላል ።

ስለዚህ የሕገ መንግሥት ጉባኤ የኢትዮጵያ ሕዝብ የጣለበትን ታላቅ አደራ በብቃት እንዲወጣ እምነቴንና መልካም ምኞቴን እየገለጽኩ ፣ በጥልቀትና በስፋት መርምራችሁ ታፀድቁት ዘንድ ሚያዚያ 25 ቀን 1986 ዓ.ም በተወካዮች ምክር ቤት የፀደቀውን የሕገ መንግሥት ረቂቅ እነሆ በታላቅ አክብሮት አስረክባለሁ ።

ክቡር ዶ/ር ፈቃደ ገዳሙ የሕዝብ ተወካዮች ምክር ቤት ምክትል ሊቀመንበር ንግግራቸውን ከጨረሱ በኋላ የሕገ መንግሥት ረቂቁን ለጉባኤው ሊቀመንበር አስረክበዋል ።

የጉባኤው ሊቀመንበር በጉባኤው ስም የኢትዮጵያ ሽግግር መንግሥት የተወካዮች ምክር ቤትን ካመሰገኑ በኋላ ጉባኤው ረቂቅ ሰነዱን የማሻሻል ወይም የማዳበር አሊያም ሌላ ረቂቅ የማዘጋጀት ሥልጣን እንዳለው አስታውሰው በቅድሚያ ረቂቅ ሕገ መንግሥቱን ለውይይት መነሻነት እንቀበል ወይም አንቀበል በሚለው ላይ ተወያይቶ መወሰን እንደሚያስፈልገው ገልጸው በጉዳዩ ላይ ሀሳብ እንዲሰጥበት ጠይቀዋል ።

በዚሁ መሠረትም ጉባኤው ጥቅምት 18 ቀን 1987 ዓ.ም ከሰዓት በኋላ ሕገ መንግሥት የማርቀቅ ሂደቱ ሆነ የጉባኤ አባላት ምርጫን ዲሞክራሲያዊነት በተመለከተ በአደረገው ውይይት 520 ዲሞክራሲያዊነቱን በመደገፍ ፣ 2 በመቃወም 5 ድምፀ ተአቅቦ በመመዝገቡ ፣ ረቂቁን ለውይይት መነሻነት መቀበሉን እንደሚያመለክት ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል አቶ አህመድ ሀሰን ገልጸዋል ።

ይህንን ሀሳብ በመደገፍ ክክልል 5 አቶ መሐሙድ ድሪር በሰጡት አስተያየት በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ፅንሰ ሐሳቦች ላይ ሕዝቡ ከቀበሌ ጀምሮ በተለይ በኢትዮጵያ ታሪክ ለመጀመሪያ ጊዜ በክልል 5 እና በክልል 2 የሚገኙ ዘላኖች ሳይቀሩ የተወያዩበት ከመሆኑም በላይ የተወካዮች ምክር ቤትም በርካታ ቀናት በመውሰድ ተወያይቶ ያሻሻለው መሆኑን ገልጸው ፣ ይህ ጉባኤ ከተወካዮች ምክር ቤት ይበልጥ ሰፊ ውክልና ለኢትዮጵያ ሕዝብ ዘላቂ ሕገ መንግሥት የማዘጋጀት ሥልጣን ያለው በመሆኑ ረቂቅ ሕገ መንግሥቱን ለውይይት መነሻነት ቢቀበለው የተሻለ እንደሚሆን አስረድተዋል ::

በሌላ በኩልም ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 ረቂቅ ሕገ መንግሥቱን ለውይይት መነሻነት መቀበሉን በመቃወም በሰጡት አስተያየት ሕዝቡ በሕገ መንግሥቱ ፅንሰ ሀሳቦች ላይ ሲወያይ እርሳቸው ከተመረጡባቸው 20 ቀበሌዎች ውጭም ተዘዋውረው ሂደቱን መመልከታቸውን ፣ ነገር ግን በቀበሌ አመራር የሚሰጠው ግምገማና ሕዝቡ ተሰብስቦ የሚናገረው የተለያየ መሆኑን ፣ ለዚህም በምሳሌ ሲያስረዱ በቀበሌ ግምገማ የራስን ዕድል በራስ መወሰን እስከ መገንጠል መሬት በመንግሥት ቁጥጥር ሥር እንዲሆንና ሰንደቅ አላማ እንዲሻሻል ሕዝቡ መደገፉን ፣ በሌላ በኩል የክልል 14 ፕሬዚዳንት ባሉበት ሕዝቡ ተጠርቶ በሰጠው አስተያየት መሬት በግል ካልተያዘ ነፃነት እንደማይሰማውና ሊዝ ከታወጀ እንደ ኤዲስ እንደሚቆጥረው መናገሩን ገልጸው ሕዝቡን ወይንስ የቀበሌ አመራር ስለሕዝብ ሆነው የሚነግሩንን እንስማ ? ሲሉ ጠይቀዋል ::

አያይዘውም በአዲስ አበባ ከተማ በወረዳ 12 ቀበሌ 06 የሕዝቡ ብዛት 17,700 ሆኖ ሳለ ለሕገ መንግሥት ፅንሰ ሀሳቦች ውይይት የተገኘው 19 ብቻ መሆኑን ፣ ከእነዚህ ውስጥም አብዛኛዎቹ ወጣቶችና ሕገ መንግሥቱን በመደገፍ በፖሊስ ሠራዊት ለመቀጠር ብለው እንደመጡ የገለጹላቸው መሆኑን ጠቁመው ሕዝቡ በሂደት ያለውን ተቃውሞ ባለመሰብሰብ መግለጹን ፣ ረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ሕዝብ ያወገዘው የአንድ ፓርቲ ሥራ እንደሆነ አመልክተዋል ::

አስከትለውም ሕዝቡ በሪፈረንደም ቢጠየቅ 10,000 አንድ እንኳን የመንግሥት ጭሰኛ ልሁን ወይም ንብረቴን መሸጥ ልክልክል የሚል እንደማይገኝና መንግሥት ዕውነታኛ ዲሞክራሲ የሚፈልግ ከሆነ የሕዝቡን ሀሳብ በቀበሌ ሳይሆን በሪፈረንደም ቢጠየቅ የተሻለ እንደሚሆን አስረድተዋል ::

ቀጥለውም ምርጫውን በተመለከተ ተቃዋሚን አስሮ ውድድር ማካሄድ በአንድ ፈረስ ለብቻ ጋልቦ እንደማሸነፍ እንደሚቆጠርና ኢ-ዲሞክራሲያዊ



መሆኑን በሂደቱ የመንግሥትና የሕዝብ ፍላጎት ቢጋጭ እሳቸው ሕዝቡን እንደሚደግፉ የኢሕአዴግ ተወካይ ግን የድርጅቱ ፍላጎት ከሕዝቡ ፍላጎት ጋር ቢጋጭ የድርጅቱን እንደሚመርጥ ጠቁመው ጉባኤው ረቂቁን ለመወያየት እንዳይቀበለው ጠይቀዋል ::

ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን በበኩላቸው ዋናው ጉዳይ ረቂቅ ሕገ መንግሥቱን ለውይይት መነሻነት እንቀበል ወይም አንቀበል የሚል ቢሆንም ከትናንት ጀምሮ በሻለቃ አድማሴ ዘለቀ የተነሱት አንዳንድ ጉዳዮች ስላሉ ለሪኮርድ መልስ መስጠት እንደሚፈልጉ ገልጸው በሳቸው እምነት ሊዝ ኤዴስ መባሉ እንዳስገረማቸውና ይህንንም የሚሉት ፖሊሲው የከነከናቸው ጥቂት ባለሀብቶችና የበፊቱ የመሬት ሥሪት እንዲመለስ የሚፈልጉ ወገኖች መሆናቸውን በአንፃሩም ሊዝ ችግር እንዳልሆነና ችግሩ ሊዝ እንዴት ይዋቀር የሚለው መሆኑን አስረድተዋል ::

አያይዘውም ለስብሰባ የወጣው ሕዝብ አንሰተኛ ነው በተባለበት ቀበሌ የወጣው ሕዝብ ከሕዝብ የወጣ እንጂ ከሌላ አለመሆኑ መታወቅ እንዳለበት ገልጸዋል ::

አስከትለውም ትናንት ስለአየር ኃይል በተወሳበት ጊዜ ምን እንዲጥል ትፈልጋላችሁ ብርትኳን ወይንስ ሚንደሪን የሚል ጉዳይ ተነስቶ እንደነበር አስታውሰው ይህንን ጉዳይ በተመለከተ መታወስ ያለበት በክልል 5 በአይሻና ደጋሀቡር ሴቶች ፣ ሕፃናትና አረጋዊያን ሳይቀሩ በቦምብ የተጨፈጨፉበት ፣ የተረፉት በሳንጃ የታረዱበት ሁኔታ መኖሩንና በቅርቡም በሐውዜን የተፈጸመውን መታሰብ እንዳለበት ፣ ነገር ግን ወደኋላ ተመልሶ ያለፉ ጉዳዮችን ለማንሳት የማይፈልጉ መሆናቸውን ፣ ተቃዋሚዎች ታስረዋል የተባለውንም በተመለከተ መንግሥት ተቃዋሚዎችን የሚያስር ቢሆን ኖሮ እዚህ ቤት ካሉ ሰዎች ጀምሮ በሚሊዮን የሚቆጠሩ ሰዎች ይታሰሩ እንደነበረ ፣ የታሰሩትም ከባድ ወንጀል ፈጽመው በፍርድ የሚጠየቁ መሆናቸውን አስገንዝበዋል ::

ቀጥሎም አቶ ሙሉጌታ ገ/ሕይወት ከክልል 1 ረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ለውይይት መነሻነት እንዲያገለግል የሚያግደው ምንም ነገር እንደሌለ ፣ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ የሕዝብ ተሳትፎ አልነበረም ሲሉ ያቀረቡት አስተያየት የምርጫ ቦርድ ካቀረበው መረጃ አንፃር የተሳሳተ መሆኑን ለምሳሌ እሳቸው በተመረጡበት ወረዳ 25,0000 ሰው በላይ ድምፅ መስጠቱንና ከእነዚህም ውስጥ 8,000 ሰው በላይ እሳቸውን መምረጡ የሕዝብ ተሳትፎ የነበረ መሆኑን እንደሚያሳይ አስረድተዋል ::

በመጨረሻም በቀበሌ የሚካሄደውም ውይይት የሕዝብ ውይይት መሆኑን መታወቅ እንዳለበትና በተወካዮች ምክር ቤት የተሻሻለው የሕገ መንግሥት ረቂቅ ሰነድ የብዙሀኑን ብቻ ሳይሆን የአናሳውንም ወገን ሀሳብ ያካተተ መሆኑን አመልክተዋል::

አቶ ረሺድ መንግሥቱ ከደቡብ ሕዝቦች ክልል አንዳንድ ሰዎች ኢሕአዴግ በሕዝብ ተወክሉ እንዳልቀረበና ሀሳብም የማቅረብ መብት እንደሌለው አድርገው አስተያየት የሚሰጡ መኖራቸውን ፣ ይህ ደግሞ መብትን እንደመጋፋት ስለሚ ቆጠር ጥንቃቄ እንዲደረግ አሳስበው ማንም ሰው ያመነበትን ዓላማ የመደገፍ መብት እንዳለው መታወቅ እንዳለበት ፣ ቤቱም ውይይቱ በተነሳው ሀሳብ ዙሪያ ብቻ ቢያካሂደው እንደሚሻል ገልጸዋል ::

በመቀጠልም የሕገ መንግሥት ኮሚሽን የተለያዩ አካሎችንና ሙያተኞችን በማርቀቁ ሂደት እንዲሳተፉ በማድረግ የሌሎች አገሮችንም ልምድ በመቅሰም እንዲሁም ሁሉም ሕዝቦች በረቂቁ ላይ ውይይት አድርገው እንዲያዳብሩት በማድረግ አርቅቆ ለተወካዮች ምክር ቤት በማቅረብ ምክር ቤቱም ረቂቁን በመገምገም ያሻሻለው መሆኑን ፣ በትናንትናው ውይይትም የረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ዝግጅት ሂደት ዲሞክራሲያዊነት የተረጋገጠ በመሆኑ ረቂቁን ለመወያያ መነሻነት እንቀበለው ሲሉ አቶ ታሪኩ ዕጌ እና አቶ መኩሪያ ታፈሰ ከክልል 14 ፣ አቶ እጅጉ ገ/ሚካኤል ፣ አቶ ተስፋዬ ፉቻላ እና አቶ ደረጀ ዳኩነች ከደቡብ ሕዝቦች ክልል በተናጠል አስተያየት ሰጥተዋል ::

ከዚያም በጉዳዩ ላይ በቂ ውይይት መደረጉን ሊቀመንበሩ ገልጸው ከቤቱ በቀረበው አስተያየት መሠረት በጉዳዩ ላይ ድምፅ እንዲሰጥበት ተደርጎ ረቂቅ ሕገ መንግሥቱን ለውይይት መነሻነት እንቀበለው የሚለውን በመደገፍ 518 ፣ በመቃወም 3 ፣ ድምፀ ተአቅቦ 1 ተመዝግቦ ረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ለውይይት መነሻነት ተቀባይነት አግኟል ::

በሌላ በኩል የጉባኤው አባላት ስለሕገ መንግሥት አረቃቅና ግንዛቤ እንዲኖራቸው የሌሎች አገሮች ልምድና በሙያው ዕውቀት ያላቸው ሰዎች የሀገሪቱን ተጨባጭ ሁኔታን በመጨመር ማብራሪያ እንዲሰጡ ቢደረግ የሚል ሀሳብ ከአቶ ዘለሌ ፀጋሥላሴ ከክልል 14 ቀርቧል ::

በማስከተልም የጉባኤውን አደረጃጀት በተመለከተ አጀንዳ የቀረበ ሲሆን አደረጃጀቱን ሆነ ውስጠ ደንቡ ከጉባኤው አመራር ቀርቦ ጉባኤው ይወያይበት የሚል ሀሳብ ከአቶ አዳሙ ደገፋው ከክልል 14 እና አቶ አባይ ፀሐዬ ከክልል 1 ያቀረቡትን ሀሳብ ለድምፅ ቀርቦ 518 የድምፅ ድጋፍ ተመዝግቦ ያለምንም ተቃውሞ ተቀባይነት አግኝቷል ::

በመጨረሻም የጉባኤው ሊቀመንበር የጉባኤው ውስጠ ደንብ አሁን ለጉባኤው አባላት እንደሚሰራጭ ገልጸው ፣ የጉባኤውን አደረጃጀት በተመለከተ አመራሩ ጥናት አድርጎ ጥቅምት 21 ቀን 1987 ዓ.ም በ2:30 ለሚቀለው ጉባኤ እንደሚያቀርብ አስታውቀው የዕለቱ ስብሰባ ከቀኑ 11:55 ሰዓት ተጠናቋል ::



ጥቅምት 21 ቀን 1987 ዓ.ም ከሚቱ በ3:00 ሰዓት የቀጠለው የሕገ መንግሥት ጉባኤ የተመራው በጉባኤው ሊቀመንበር በዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ሲሆን በዕለቱ የቀረበው አጀንዳም የጉባኤውን አደረጃጀት የሚመለከት ነበር ::

በመጀመሪያ ሊቀመንበሩ የጉባኤውን አደረጃጀት በሚመለከት የአመራር አካሉ የመንደርደሪ ሀሳብ ይዞ መቅረቡን ጠቁመው ይህም በጉባኤው ምክትል ፀሐፊ በአቶ አባተ ኪሾ እንደሚገለጽ አስታውቀዋል ::

በዚህም መሠረት አቶ አባተ ኪሾ አመራሩ የጉባኤውን አደረጃጀት በማጥናት ኮሚቴዎች ማቋቋም እንደሚገባው መገንዘቡን ጠቁመው የኮሚቴዎች አስፈላጊነትም ሲያብራሩ ፣

1. ጉባኤው የተለያዩ ብሔር /ብሔረሰቦች እና እናሳ ብሔሮች ፣ ግለሰቦችና የፖለቲካ ድርጅቶች ያሉበት በመሆኑ ተሳትፎአቸውን ለማስፋት ፣
2. ከጉባኤው ውስጥም ሆነ ከጉባኤው ውጭ የጉባኤውን ተልዕኮ ለማሳካት ፣
3. ረቂቅ ሕገ መንግሥቱ በርካታ አንቀጾች ያሉት በመሆኑ በኮሚቴ ተከፋፍሎ በጥልቀት ለመመርመር እንዲቻል ፣

የሚሉትን ምክንያቶች ጠቅሰዋል ::

አያይዘውም ከረቂቅ ሕገ መንግሥቱ አበይት ክፍሎችን በማገናት 10 ኮሚቴዎች እንዲቋቋሙ የጉባኤው አመራር አስፈላጊ መሆኑ ያመነበት መሆኑን ገልጸው እነዚህም

1. የሰብአዊና የዲሞክራሲያ መብት ኮሚቴ
2. የብሔር/ብሔረሰቦች መብት ኮሚቴ
3. የንብረትና የኢኮኖሚ መብት ኮሚቴ
4. የፌዴራልና የክልል ሥልጣን ክፍፍል ኮሚቴ
5. የፕሬዚዳንትና የጠቅላይ ሚኒስትር ጉዳይ ኮሚቴ
6. የፍርድ ቤቶች ጉዳይ ኮሚቴ
7. የብሐራዊ ፖሊሲ መርሆዎች ኮሚቴ
8. የታክስና ግብር ጉዳዮች ኮሚቴ
9. የሕገ መንግሥት ቅርፅ ኮሚቴ
10. የሴቶች ጉዳይ ኮሚቴ

መሆናቸውንና እያንዳንዱ ኮሚቴ 11 አባላት እንደሚኖረው ገልጸዋል ::

አቶ አባተ ኪሾ አስከትለውም አመራረጣቸውን በተመለከተ ሲገልጹ የኮሚቴዎች ስብሳቢዎች ከጉባኤው ቋሚ አመራር አባላት ጋር ሆነው አብረው ስለሚሠሩ በሚስጥር የድምፅ አሰጣጥ ፣ ሌሎች የኮሚቴው አባላት ግን እጅ በማውጣት እንደሚመረጡ ጠቁመው ለያንዳንዱ ኮሚቴ 10 አባላት ለመምረጥ 13 ዕጩዎች እንደሚጠቆሙ አብራርተዋል ::

ቀጥሎም ሊቀመንበሩ የጉባኤውን አደረጃጀት በሚመለከት በአቶ አባተ ኪሾ የቀረበውን ፣

. ስለኮሚቴዎች አስፈላጊነት ፣

. ስለኮሚቴዎች ብዛት እና ፣

. የአባላት ብዛትና አመራረጥ ፣

አስመልክቶ የተለያዩ አስተያየት ካሉ ሊቀርብ እንደሚችል ቢያሳስቡም ባለመቅረቡ የቀረበውን ሀሳብ በመደገፍ አስተያየት እንዲሰጥ ጠይቀዋል ::

በዚሁም መሠረት ከክልል 5 ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ፣ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል አቶ ኤሊያስ ተሮ ፣ ከክልል 14 አቶ አብዱራዛቅ መሐመድ እና አቶ አለሙ እንቁ ፣ ከክልል 13 ሐጂ አብዱራህማን አብዱርቃድር የኮሚቴዎችን አስፈላጊነት ፣ ብዛትና የአባላት ቁጥር እንደሚደግፉ ገልጸው የኮሚቴዎቹ አወቃቀር ረቂቅ ሕገ መንግሥቱን በጥልቀት ለማየትና ለመመርመር እንደሚያስችል አመልክተዋል ::

በሌላ በኩል የጉባኤው ዋና ፀሐፊ የኮሚቴዎች ሰብሳቢዎች በሚጥር ድምፅ አሰጣጥ ከተመረጡ በኋላ ማን ለየትኛው ኮሚቴ ሰብሳቢ እንደሚሆን ከጉባኤው አመራር ጋር በመመካከር ድልድሉ እንደሚከናወን ገልጸዋል::

በኮሚቴዎች አስፈላጊነት ፣ ብዛትና የአባላት ቁጥር ላይ የጉባኤው አባላት ድጋፍ በድምፅ እንዲገለጽ ተጠይቆ ከአንድ ተቃውሞ በስተቀር በተቀሩት ሁሉ ተደግፏል ::

በመቀጠልም የኮሚቴዎች ሰብሳቢዎችና የጉባኤው አመራር አካል የሚሆኑትን 10 ሰዎችን ለመምረጥ 13 ሰዎች እንዲጠቆሙ ተደርጓል :: እያንዳንዱ ዕጩ ተወዳዳሪ ከተጠቆመ በኋላ የሕይወት ታሪኩ ፣ በተመረጠበት ለማገልገል ያለውን ፍላጎት ገልጾ ድጋፍ ሲጠየቅለት ከጉባኤው አባላት 1/3ኛና ከዚያም በላይ ያገኙት ዕጩ ሆነው ተመዝግበዋል ::

ምርጫው በሚስጥር ድምፅ አሰጣጥ ከመካሄዱ በፊትም የጉባኤውን አመራር እንዲያግዙና ድምፅ እንዲቆጥሩ ፣



1. አቶ ሱፊያን አህመድ ከክልል 4
2. አቶ ካሚል አህመድ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል
3. ኢ/ር ሐሰን ኢብራሂም ከክልል 5
4. አቶ መኩሪያ ታፈሰ ከክልል 14
5. አቶ ገዙ አሸቴ ከክል 3

ከጉባኤው አባላት መካከል ተመርጠዋል ::

ከዚያም የድምፅ አሰጣጡ እንዲቀጥልና እያንዳንዱ የጉባኤው አባል ድምፅ ከሰጠ በኋላ መውጣት እንደሚችል ሊቀመንበሩ ጠቁመው የከሰዓት በኋላ ስብሰባም ከቀኑ 9:00 ሰዓት እንደሚጀመር ገልጸዋል ::

ጉባኤው ከምሳ በኋላ ስብሰባው በምርጫው ውጤት ላይ ውይይቱን የቀጠለ ሲሆን በመጀመሪያ የጉባኤው ሊቀመንበር በጉባኤው 530 አባላት በምርጫው ወቅት እንደተመዘገቡ ፣ ከእነዚህም ውስጥ 529 ሰዎች በምርጫው ቢሳተፉም 11 የጉባኤው አባላት የምርጫውን ቴክኒካሊቲ ሳያሟሉ በመቅረታቸው የሰጡት ድምፅ ውድቅ እንደሆነ አስረድተው የምርጫውን ውጤት ገልጸዋል ::

በዚሁም መሠረት ፣

1. ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ከክልል 4 520 ድምፅ በማግኘት 1ኛ
2. ኢ/ር አቢያሌ ፍላቴ ከክልል 6 495 ድምፅ በማግኘት 2ኛ
3. ወ/ሮ እንወይን ገ/መድህን ከክልል 3 492 ድምፅ በማግኘት 3ኛ
4. አቶ ሀሰን አሊ ከክልል 4 492 ድምፅ በማግኘት 3ኛ
5. ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ ከክልል 1 490 ድምፅ በማግኘት 4ኛ
6. አቶ አህመዲን ኢብራሂም ከክልል 4 482 ድምፅ በማግኘት 5ኛ
7. አቶ ታደሰ ካሳ ከክልል 3 481 ድምፅ በማግኘት 6ኛ
8. አቶ ዩሱፍ መሐመድ አይሪ ከክልል 2 471 ድምፅ በማግኘት 7ኛ
9. አቶ አህመድ ሀሰን ከደቡብ ኢት/ሕዝቦች ክልል 460 ድምፅ በማግኘት 8ኛ
10 አቶ ግርማ ብሩ ከክልል 4 407 ድምፅ በማግኘት 9ኛ

ሆነው ወደፊት ለሚቋቋሙት 10 ኮሚቴዎች በሰብሳቢትና የጉባኤው አመራር አካል ሆነው ተመርጠዋል ::

በሌላ በኩል ከዕጩዎች መካከል

አቶ አሊ አብዶ ከክልል 14 118 ድምፅ

አቶ ደረጀ ዳኬጎዶ ከደቡብ ኢት/ሕዝቦች ክልል 88 ድምፅ

ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 64 ድምፅ

በማግኘታቸው ሳይመረጡ ቀርተዋል ::

በማግኘታቸው ሳይመረጡ ቀርተዋል :: ከላይ ከተራ ቁጥር 1-10 የተዘረዘሩት አባላት በከፍተኛ ድምፅ የተመረጡት ከላይ ከተራ ቁጥር 1-10 የተዘረዘሩት አባላት ከአመራሩ ጋር በመሆን ማን የትኛውን ኮሚቴ ሰብሳቢ እንደሚሆን ጥቂት ከተመካከሩ በኋላ ሰፊ ጊዜ ወስዶ በመመካከር የሥራ ድልድሉን ለማድረግ ስለተስማሙ ድልድሉ ለሌላ ጊዜ መተላለፉን ሊቀመንበሩ ገልጸዋል ::

በማስከተልም ጉባኤው ለ10 ኮሚቴዎች ለእያንዳንዳቸው 10 አባላት ለመመረጥ ጉባኤው በዚቱ ስብሰባ በተስማማበት መሠረት ምርጫው እንደሚቀጥል ሊቀመንበሩ ገልጸው የአንድ ኮሚቴ 10 አባላትን ለመምረጥ 13 ዕጩዎች እንዲቀርቡና ዕጩ እንደሆኑ ፣ የሚጠቆሙ ሰዎችም ራሳቸውን ለጉባኤው እንዲያስተዋውቁ ፣ እንዲሁም ዕጩ ሆነው ለመመዝገብ በጉባኤው አባላት ቢያንስ 1/3ኛው መደገፍ እንደሚገባቸው አስገንዝበዋል ::

በዚህም መሠረት ፣

ለሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብቶች ኮሚቴ አባልነት ከተጠቆሙት ሰዎች መካከል 1/3ኛውና ከዚያም በላይ ድምፅ ያገኙት ዕጩ አባላት ተጠቁመው ምርጫው እጅ በማውጣት ቀጥሎ በሂደት ለአንድ ዕጩ ተወዳዳሪ መጠየቅ ያለበት ድጋፍ እንጂ ተቃውሞና ድምፀ ተአቅቦ መታከል እንደሌለባቸው ሀሳብ ቀርቦ በዚሁ ሀሳብ ላይ ቤቱ እንዲወስን ለድምፅ ቀርቦ በምርጫው ወቅት ተቃውሞና ድምፀ ተአቅቦ መጠየቅ የለበትም የሚለው ሀሳብ ከፍተኛ ድጋፍ አግኝቷል ::

ከዚያም ለሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብቶች ኮሚቴ አባልነት የቀረቡት ዕጩዎች ምርጫ ቀጥሎ ፣

1.አቶ ወንድሙ ተሮ ከደቡብ ኢት/ ሕዝቦች ክልል /ብሔረሰብ ገዲኦ/ 510 ድምፅ በማግኘት 1ኛ

2.አቶ ዳንኤል ደሴ ከክልል 4 /ብሔረሰብ ኦሮሞ/ 507 ድምፅ "" 2ኛ

3. ዶ/ር ግርማ ከበደ ከክልል 3 /ብሔረሰብ አማራ/ 501 ድምፅ "" 3ኛ

4. አቶ በሽር ሼህ ሰኢድ ከክልል6/ብሔረሰብ ቤንሻንጉል / 501 ድምፅ "" 3ኛ

5. አቶ ሳህሌ ገራር ከክልል 1 /ብሔረሰብ ትግራይ/ 496 ድምፅ "" 4ኛ



6. ዶ/ር ተከተል ፎርሲዶ ከደቡብ ኢት/ ሕዝቦች ክልል /ብሔረሰብ ከንባታ/ 494 ድምፅ "" 5ኛ

7. . ዶ/ር አዲሱ ለማ ከክልል 4 /ብሔረሰብ ኦሮሞ/ 494 ድምፅ "" 6ኛ

8. አቶ አቡበከር ሙሳ ከክልል 2 /ብሔረሰብ አፋር/ 459 ድምፅ "" 7ኛ

9. አቶ አብዱራህማን አብዱርቃድር ከክልል 13/ /ብሔረሰብ ሐረሪ / 458 ድምፅ "" 8ኛ

10. አቶ ከራር ዩሱፍ ክልል 6 /ብሔረሰብ ቤንሻንጉል / 458 ድምፅ "" 9ኛ

ሆነው ለኮሚቴ አባልነት የተመረጡ ሲሆን ከቀረቡት ዕጩዎች መካከል ፣

1. ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 170 ድምፅ
2. አቶ ኢብራሂም አህመድ ከክልል 6 132 ድምፅ
3. አቶ ዴቪድ ኢከወር ከክልል 12 83 ድምፅ

በማግኘት ለኮሚቴ አባልነት ሳይመረጡ ቀርተዋል ::

ጉባኤው የሌሎች ኮሚቴዎች አባላትን ምርጫ ለመቀጠል ቢፈልግም በዕለቱ ጊዜው እንደማይበቃ በመገንዘቡ የዕለቱን ስብሰባ 11:30 አብቅቷል ::

ጥቅምት 22 ቀን 1987 ዓ.ም ከሟቱ 3 00 ሰዓት በኢትዮጵያ ሕገ መንግሥት ጉባኤ የተመራው በጉባኤው ጉባኤ አጻራሽ የቀጠለው የኢትዮጵያ ሕገ መንግሥት ጉባኤ የተመራው በጉባኤው ሊቀመንበር በዶ/ር ጋሰ ጊዳዳ ሲሆን በዕለቱ የቀረበው አጀንዳም ፤

1. የጉባኤውን ኮሚቴዎች ሊቃነመናብርት ድልድል ስለመግለጽ ፤

2. የኮሚቴዎች አባላት ምርጫ ማካሄድ ፤

2. የኮሚቴዎች አባላት ምርጫ ማካሄድ ፤ የሚል እንደሆነ ሰብሳቢው ገልጸው በቅድሚያ የኮሚቴዎቹን ሊቃነመናብርት ድልድል ዝርዝር እንደሚከተለው ቀርቧል ::

| | |
|---|---|
| 1. ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ | የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብቶች ኮሚቴ ሰብሳቢ |
| 2. ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን | የብሔር/ብሔረሰቦች ኮሚቴ ሰብሳቢ |
| 3. አቶ ግርማ ብሩ | የንብረትና የኢኮኖሚ ኮሚቴ ሰብሳቢ |
| 4. አቶ ሀሰን አሊ | የፌደራልና የክልል ሥልጣን ክፍፍል ኮሚቴ ሰብሳቢ |
| 5. አቶ ዩሱፍ መሐመድ | የፕሬዚዳንትና ጠቅላይ ሚኒስትር ጉዳይ ኮሚቴ ሰብሳቢ |
| 6. አቶ አህመዲን ኢብራሂም | የፍርድ ቤቶች ጉዳይ ኮሚቴ ሰብሳቢ |
| 7. አቶ ታደሰ ካሳ | የብሔራዊ ፖሊሲ መርሆዎች ኮሚቴ ሰብሳቢ |
| 8. አቶ አህመድ ሀሰን | የግብርና ታክስ ጉዳይ ኮሚቴ ሰብሳቢ |
| 9. ኢ/ር አብያሌ ፍሳቴ | የሕገ መንግሥት ቅርፅ ኮሚቴ ሰብሳቢ |
| 10. ወ/ሮ እንወይን ገ/መድህን | የሴቶች ጉዳይ ኮሚቴ ሰብሳቢ |

እንደሆኑ ሊቀመንበሩ ጠቁመው በድልድሉ ላይ አስተያየት ካለ ሊቀርብ እንደሚችል አሳስበዋል ::

በዚህም መሠረት የተለያዩ የጉባኤው አባላት ድልድሉ አግባብ መሆኑን አስተያየት ከሰጡ በኋላ በጉባኤው እንዲፀድቅ ለድምፅ ቀርቦ በሙሉ ድምፅ ተደግፏል :: የኮሚቴዎች ሊቃነመናብርት የጉባኤው አመራር አካል እንደሆኑ የጉባኤው ሊቀመንበር ገልጸዋል ::

በመቀጠልም ሊቀመንበሩ የእያንዳንዱ ኮሚቴ 10 አባላት ለመምረጥ ጥቆማ ከመሰጠቱ በፊት ለአንድ ኮሚቴ 13 ዕጩ አባላት እንደሚጠቆሙ ፤ ተጠቋሚዎች የራሳቸውን የሕይወት ታሪክ በአጭሩ እንደሚገልጹና በዕጩነት ለመመዝገብ 1/3ኛና ከዚያ በላይ ማግኘት እንደሚገባ አሳስበው የጉባኤው አባላት ከ13 ዕጩ አባላት መካከል እንደሚመረጡ አስገንዝበዋል ::

በዚህም መሠረት ጥቆማው ከተካሄደና እያንዳንዱ ተጠቋሚ የሕይወት ታሪኩን በአጭሩ እንዲገልጽ ከተደረገ በኋላ በ1/3ኛና ከዚያ በላይ በሆነ የጉባኤው አባላት ድምፅ ያገኙ 13 ዕጩዎች ተመዝግበው ምርጫው እጅ በማውጣት ተካሂዷል ::



2. የብሔር/ብሔረሰቦች መብት ኮሚቴ

ለብሔር/ብሔረሰቦች ኮሚቴ ዕጩ አባል ሆነው ከቀረቡት መካከል ፤

1. አቶ ደበበ አበራ ከደቡብ ኢት/ ሕዝቦች ክልል /ብሔረሰብ ፣ከፍች / 484 ድምፅ በማግኘት 1ኛ

2. ዶ/ር አደም ኢብራሂም ከክልል 4 /ብሔረሰብ ፣ኦሮሞ / 482 ድምፅ በማግኘት 2ኛ

3. አቶ መሐመድ አሳው ከክልል 2 /ብሔረሰብ ፣አፋር/ 482 ድምፅ በማግኘት 2ኛ

4. አቶ ደመቀ መኮንን ከክልል 3 /ብሔረሰብ ፣አማራ/ 482 ድምፅ በማግኘት 2ኛ

5. አቶ አብዱራሂም መሐመድ ከክልል 6 /ብሔረሰብ ፣ቤንሻጉል/ 474 ድምፅ በማግኘት 3ኛ

6. አቶ ሙሉጌታ ገ/ሕይወት ከክልል 1 /ብሔረሰብ ፣ትግራይ/ 468 ድምፅ በማግኘት 4ኛ

7. ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 /ብሔረሰብ ፣አማራ/ 468 ድምፅ በማግኘት 4ኛ

8. አቶ ዴቪድ ኡከወር ከክልል 12 /ብሔረሰብ ፣አኝዋክ/ 464 ድምፅ በማግኘት 5ኛ

9. አቶ ወዕሊቦ አሰፋ ከደቡብ ኢት/ ሕዝቦች ክልል /ብሔረሰብ ፣አኝዋክ/ 460 ድምፅ በማግኘት 6ኛ

10. አቶ ዑመር አብዱልሠታር ከክልል 13 /ብሔረሰብ ፣ሐረሪ/ 445 ድምፅ በማግኘት 7ኛ

የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብቶች ኮሚቴ አባላት ሆነው ሲመረጡ ፤

| | | |
|---|---|---|
| አቶ ኃይሉ ገመዳ | ከክልል 4 | 133 ድምፅ |
| አቶ ኢብራሂም ዘካሪያ | ከክልል 13 | 97 ድምፅ |
| አቶ አብዱራዛቅ መሐመድ | ከክልል 14 | 37 ድምፅ |

በማግኘታቸው ሳይመረጡ ቀርተወሰል ::

3. <u>የንብረትና የኢኮኖሚ መብት ኮሚቴ፤</u>

ለንብረትና ኢኮኖሚ ኮሚቴ ከተመዘገቡት 13 ዕጩ አባላት መካከል ፤

1. አቶ ሀመድ አሊ ከክልል 2 /ብሔረሰብ አፋር/ 491 ድምፅ በማግኘት 1ኛ

3. ወ/ሮ ኑሪያ መሐመድ ከክልል 1 ብሔረሰብ ትግራይ/ 491 ድምፅ በማግኘት 1ኛ

3. አቶ ሱፊያን አህመድ ከክልል 4 /ብሔረሰብ ኦሮሞ/
491 ድምፅ በማግኘት 1ኛ

4. አቶ አብዱራሂም ሐጂ ሁሴን ከክልል 6 /ብሔረሰብ ቤንሻንጉል/
486 ድምፅ በማግኘት 2ኛ

5. አቶ ሀሰን ኢብራሂም ከክልል 5 6 /ብሔረሰብ ሶማሌ/
486 ድምፅ በማግኘት 3ኛ

6 አቶ ዓለሙ አስፋው ከክልል 3 /ብሔረሰብ አማራ /
479 ድምፅ በማግኘት 4ኛ

7. አቶ ካራቴ ጉሎ ከደቡብ ኢት/ ሕዝቦች ክልል ብሔር ኮንሶ/
472 ድምፅ በማግኘት 5ኛ

8. አቶ ጴጥሮስ ማርኮ ከደቡብ ኢት/ ሕዝቦች ክልል /ብሔርሰብ ቀቢና/
463 ድምፅ በማግኘት 5ኛ

9. አቶ ታሪኩ ዕጌ ከክልል 14 /ብሔርሰብ አማራ/
451 ድምፅ በማግኘት 6ኛ

10. አቶ ተመሳ ብሩ ከደቡብ ኢት/ ሕዝቦች ክልል /ብሔርሰብ ጋሞ/
441 ድምፅ በማግኘት 5ኛ

ሆነው ለንብረትና ኢኮኖሚ መብት ኮሚቴ ሲመረጡ ፣

| | | |
|---|---|---|
| አቶ ሽፈራው ገለታ | ከደቡብ ኢት/ ሕዝቦች ክልል | 145 ድምፅ |
| አቶ ጫላ ወርዶፋ | ከክልል 4 | 137 ድምፅ |
| አቶ ሙደር ሰማን | ከደቡብ ኢት/ ሕዝቦች ክልል | 70 ድምፅ |

በማግኘታቸው ሳይመረጡ ቀርተዋል ።

ከዚያም ጉባኤው ለሻይ ዕረፍት ተነስቷል ።

ከሻይ ዕረፍት በኋላ የሌሎች ኮሚቴዎች አባላት ምርጫ ቀጥሏል ።

3. የፌዴራልና የክልል ሥልጣን ክፍፍል ኮሚቴ አባልነት ጥቆማ ተካሂዶ ከተመዘገቡት 13 ዕጩዎች መካከል ፣

1. አቶ አባስ አዙቤር ከክልል 6 /ብሔረሰብ ቤንሻንጉል/
504 ድምፅ በማግኘት 1ኛ

2. አቶ ወይናቶ አበራ ከክልል 12 /ብሔረሰብ መዠንገር/
497 ድምፅ በማግኘት 2ኛ

3. አቶ ዳትራ ዳራ ከደቡብ ኢት/ ሕዝቦች ክልል /ብሔረሰብ ሲዳማ/
496 ድምፅ በማግኘት 3ኛ



4 አቶ ሸምሰዲን አህመድ ከክልል 5 /ብሔረሰብ ሶማሌ/
493 ድምፅ በማግኘት 4ኛ

5. አቶ መኮንን ከበደ ከክልል 4 /ብሔረሰብ ኦሮሞ/
492 ድምፅ በማግኘት 5ኛ

6. አቶ ኃይለ ሐለፎም ከክልል 14 /ብሔረሰብ ትግራይ/
481 ድምፅ በማግኘት 6ኛ

7. አቶ ገዙ እሸቴ ከክልል 3 /ብሔረሰብ አማራ/
476 ድምፅ በማግኘት 7ኛ

8. አቶ ታደሰ ዓለማየሁ ከደቡብ ኢት/ ሕዝቦች ክልል /ብሔረሰብ ሐድያ/
472 ድምፅ በማግኘት 8ኛ

9. አቶ መሐመድ ሞድአዴ ከክልል 2 /ብሔረሰብ አፋር/
467 ድምፅ በማግኘት 9ኛ

10. አቶ አህመድ ኡስማን ከድሬዳዋ ልዩ ብሔረሰብ ኦሮሞ/
436 ድምፅ በማግኘት 9ኛ

የፌዴራልና የክልል ሥልጣን ክፍፍል ኮሚቴ አባላት ሆነው ሲመረጡ ፣

| | | |
|---|---|---|
| አቶ ሰይድ ሬድዋን | ከደቡብ ኢት/ ሕዝቦች ክልል | 50 ድምፅ |
| አቶ መሐመድ ጣሂር | ከክልል 5 | 38 ድምፅ |
| አቶ ማሞ ኡጣይሌ | ከደቡብ ኢት/ ሕዝቦች ክልል | 36 ድምፅ |

በማግኘታቸው ሳይመረጡ ቀርተዋል ።

ቀጥሎም አንድ የጉባኤው አባል ለድምፅ የሚቀርቡት ዕጩ የኮሚቴ አባላት በተመዘገቡበት ተራ መሆኑ ቀርቶ ከላይ ፣ ከታችና ከመሀል ሆኖ እንዲቀርብ የሰጡት ማሳሰቢያ ሊቀመንበሩ በመቀበል ጉባኤው ከቀኑ 6:45 ሰዓት ለምሳ ተነስቷል ።

ከሰዓት በኋላ ጉባኤው በ9:10 ሰዓት ሥራውን ጀምሮ በሌሎች ኮሚቴዎች አባላት ምርጫ ላይ ውይይቱን ቀጥሏል ፣

5. <u>የፕሬዚዳንትና ጠቅላይ ሚኒስትር ጉዳይ ኮሚቴ</u> ፣

የፕሬዚዳንትና ጠቅላይ ሚኒስትር ጉዳይ ኮሚቴ አባልነት ጥቆማ ተካሂዶ ከተመዘገቡት 13 ዕጩዎች መካከል ፣

1. አቶ መኮንን ነጋ ከክልል 4 /ብሔረሰብ ኦሮሞ/
491 ድምፅ በማግኘት 1ኛ

2. አቶ ታምራት በየነ ከደቡብ ኢት/ሕዝቦች ክልል /ብሔረሰብ ጌዲኦ/

472 ድምፅ በማግኘት 2ኛ

3. አቶ አብዱመሊክ መሐመድ ከክልል 5 /ብሔረሰብ ሶማሌ/
470 ድምፅ በማግኘት 3ኛ

4. አቶ አባይ ወልዱ ከክልል 1 /ብሔረሰብ ትግራይ/
467 ድምፅ በማግኘት 4ኛ

5. አቶ ወጌ ሳሶ ከደቡብ ኢት/ሕዝቦች ክልል /ብሔረሰብ ቡርጂ/
466 ድምፅ በማግኘት 5ኛ

6. አቶ ኒሃጋች ዲንግ ከክልል 12 /ብሔረሰብ ኑኤር/
459 ድምፅ በማግኘት 6ኛ

7. አቶ ጫላ ወርዶፋ ከክልል 4 /ብሔረሰብ ኦሮሞ/
458 ድምፅ በማግኘት 7ኛ

8. አቶ እንዳወቀ ገላው ከክልል 3 /ብሔረሰብ አማራ/
458 ድምፅ በማግኘት 7ኛ

9. አቶ ሙሉጌታ ሰይድ ከክልል 3 /ብሔረሰብ አማራ/
457 ድምፅ በማግኘት 8ኛ

10. አቶ ካሚል አህመድ ከደቡብ ኢት/ሕዝቦች ክልል /ብሔረሰብ ጉራጌ/
453 ድምፅ በማግኘት 5ኛ

ለፕሬዚዳንትና ጠቅላይ ሚኒስትር ጉዳይ ኮሚቴ አባልነት የተመረጡ ሲሆን ፣

1. አቶ ገዝሙ ቀልቦ ከደቡብ ኢት/ሕዝቦች ክልል 131 ድምፅ
2. አቶ አበበ ጎበና ከደቡብ ኢት/ሕዝቦች ክልል 36 ድምፅ
3. አቶ ኑሪ ሞሳ ከደቡብ ኢት/ሕዝቦች ክልል 23 ድምፅ

በማግኘታቸው ሳይመረጡ ቀርተዋል ::

6. <u>የፍርድ ቤቶች ጉዳይ ኮሚቴ</u>

ለፍርድ ቤቶች ጉዳይ ኮሚቴ ከተጠቆሙት 13 ዕጩዎች መካከል ፣

1. አቶ ታደሰ ወርዶፋ ከክልል 4 /ብሔረሰብ ኦሮሞ/
496 ድምፅ በማግኘት 1ኛ

2. አቶ ልጅዓለም ወልዴ ከክልል 3 /ብሔረሰብ አማራ/
476 ድምፅ በማግኘት 2ኛ

3. አቶ ተቢብ ኡስማን ከክልል 2 /ብሔረሰብ አፋር/
462 ድምፅ በማግኘት 3ኛ

4. አቶ ማሙዬ ገ/ሚካኤል ከደቡብ ኢት/ሕዝቦች ክልል /ብሔረሰብ
458 ድምፅ በማግኘት 4ኛ



5 አቶ መሀሙድ ድሪር ከክልል 5 /ብሔረሰብ ሶማሌ/
452 ድምፅ በማግኘት 5ኛ

6. አቶ ምህረቴ ሁርቃ ከደቡብ ኢት/ሕዝቦች ክልል /ብሔረሰብ ዲዝ/
444 ድምፅ በማግኘት 6ኛ

7. አቶ ዮናስ ጀረኔ ከደቡብ ኢት/ሕዝቦች ክልል /ብሔረሰብ ጎፋ/
441 ድምፅ በማግኘት 7ኛ

8. አቶ ዲሉ ኢዲሶ ከደቡብ ኢት/ሕዝቦች ክልል /ብሔረሰብ ማረቆ/
400 ድምፅ በማግኘት 8ኛ

9. አቶ አብዱራዛቅ መሐመድ ከክልል 14 /ብሔረሰብ ኦሮሞ/
400 ድምፅ በማግኘት 9ኛ

10. አቶ አበበ ጎበና ከክልል 6 /ብሔረሰብ ሽናሻ/
336 ድምፅ በማግኘት 9ኛ

ለፍርድ ቤቶች ጉዳት ኮሚቴ አባልነት ሲመረጡ ፣

1. አቶ ሀሰን በከር ከክልል 4 127 ድምፅ
2. አቶ ቀኝያለው ሃሌ ከደቡብ ኢት/ሕዝቦች ክልል 122 ድምፅ
3. አቶ ከድር መሐመድ ከክልል 4 54 ድምፅ

በማግኘታቸው ሳይመረጡ ቀርተዋል :: ጉባኤው በ10:55 ሰዓት ለሻይ ዕረፍት ተኗቷል ::

ጉባኤው ከሻይ ዕረፍት መልስ የተቀሩት ኮሚቴዎች አባላት ጥቆማና ምርጫ ያካሄደ ሲሆን በመጀመሪያ ፣

7. <u>የብሔራዊ ፖሊሲ መርሆዎች ኮሚቴ</u>

ለብሔራዊ ፖሊሲ መርሆዎች ኮሚቴ አባላት ጥቆማ ተካሂዶ ከተመዘገቡት ዕጩዎች መካከል ፣

1.ፕሮፌሰር ጀማል አብዱልቃድር ከክልል 4 /ብሔረብ ኦሮሞ/
491 ድምፅ በማግኘት 1ኛ

2. ዶ/ር አረጋዊ አክሊሉ ከክልል 1 /ብሔረብ ትግራይ/
460 ድምፅ በማግኘት 2ኛ

3. አቶ ሙደር ሰማን ከደቡብ ኢት/ሕዝቦች ክልል /ብሔረሰብ ቀቢና/
456 ድምፅ በማግኘት 3ኛ

4. አቶ ቀኝያለው ሃሌ ከደቡብ ኢት/ሕዝቦች ክልል /ብሔረሰብ ትረሺ/
455 ድምፅ በማግኘት 4ኛ

5. አቶ ግርማ ታደሰ ከክልል 14 /ብሔረብ አማራ/
451 ድምፅ በማግኘት 5ኛ

6. ዶ/ር ሙክታር ረሺድ ከክልል 4 /ብሔረብ ኦሮሞ/
448 ድምፅ በማግኘት 6ኛ

7. አቶ ማትዮስ መንታሞ ከደቡብ ኢት/ሕዝቦች ክልል /ብሔረሰብ ጠንባሮ/
446 ድምፅ በማግኘት 7ኛ

8. አቶ ትግሬ በሻ ከደቡብ ኢት/ሕዝቦች ክልል /ብሔረሰብ ከሽከ/
437 ድምፅ በማግኘት 8ኛ

9. አቶ ፀጋዬ ገለታ ከደቡብ ኢት/ሕዝቦች ክልል /ብሔረሰብ ሚኒት/
429ድምፅ በማግኘት 9ኛ

10. አቶ አለማ ምስጋና ከክልል 1 /ብሔረብ ኢሮብ/
374 ድምፅ በማግኘት 10ኛ

የብሔራዊ ፖሊሲ መርሆዎች ኮሚቴ አባላት ሆነው ሲመረጡ ፣

1. አቶ ተሰማ ጋዲሳ ከክልል 4 134 ድምፅ
2. አቶ አሊ አብዶ ከክልል 14 101 ድምፅ
3. መ/ር ዓለሙ እንቁ ከክልል 14 83 ድምፅ

በማግኘታቸው ሳይመረጡ ቀርተዋል ።

በመጨረሻም ሊቀመንበሩ የኢትዮጵያ ሕገ መንግሥት ጉባኤ አዳራሽ ግቢ ከምሽቱ 4:00 ሰዓት ላይ የሚዘጋ መሆኑና ከዚያ ሰዓት በኋላ ማንም መውጣትና መግባት እንደማይቻል ማሳሰቢያ ሰጥተው የዕለቱ ጉባኤ ከምሽቱ 12:10 ሰዓት ተጠናቋል ።





ጥቅምት 23 ቀን 1987 ዓ.ም ከጧቱ 3:00 ሰዓት በሕገ መንግሥት ጉባኤ አዳራሽ ?ቀጠለው የኢትዮጵያ ሕገ መንግሥት ጉባኤ የተመራው በሊቀመንበሩ በዶ/ር ነጋሶ ጋዳዳ ኒሆን አጀንዳውም የቀሪዎቹ የኮሚቴዎች አባላት ምርጫ ማካሄድ ነበር ።

8. <u>የግብርና የታክስ ጉዳይ ኮሚቴ</u>

በዕለቱ በቅድሚያ የግብርና የታክስ ጉዳይ ኮሚቴ አባላትን ለመምረጥ ጥቆማ ተካሂዶ ተጠቋሚዎቹ ራሳቸውን ለጉባኤው አባላት በአጭሩ አስተዋወቁ በኋላ ከጉባኤው 1/3ኛና ዚያም በላይ የድጋፍ ድምፅ በማግኘት ከተመዘገቡ ዕጩዎች መካከል ፣

1. አቶ መሐመድ አህመድ ከክልል 5 /ብሔረሰብ ሶማሌ/
483 ድምፅ በማግኘት 1ኛ

2 አቶ ተስፋዬ ሐጎስ ከክልል 1 /ብሔረሰብ ትግራይ /
483 ድምፅ በማግኘት 1ኛ

3. አቶ ተጫኔ ተፈራ ከክልል 3 ኦሮሚያ ዞን /ብሔረሰብ ኦሮሞ /
479 ድምፅ በማግኘት 2ኛ

4. አቶ መሠረት ተሾመ ከክልል 14 /ብሔረሰብ አማራ /
472 ድምፅ በማግኘት 3ኛ

5. አቶ ሙክታር መሐመድ ከክልል 4 /ብሔረሰብ ኦሮሞ /
471 ድምፅ በማግኘት 4ኛ

6. አቶ ቴዎድሮስ ባካፋ ከክልል 3 /ብሔረሰብ አማራ /
468 ድምፅ በማግኘት 5ኛ

7. አቶ ዓለማየሁ ዓለሙ ከደቡብ ኢት/ሕዝቦች ክልል /ብሔረሰብ ሸኮ/
459 ድምፅ በማግኘት 6ኛ

8. አቶ ጃቤሳ ጃጊ ከደቡብ ኢት/ሕዝቦች ክልል /ብሔረሰብ ወላይታ/
459 ድምፅ በማግኘት 7ኛ

9. አቶ አህመድ ሞዴአዴ ከክል 2 / ብሔረሰብ አፋር/
441 ድምፅ በማግኘት 8ኛ

10. አቶ ኃይለማርያም ተክሌ ከደቡብ ኢት/ሕዝቦች ክልል /ብሔረሰብ ባስኬቶ/
412 ድምፅ በማግኘት 7ኛ

ለግብርና ታክስ ጉዳይ ኮሚቴ አባልነት የተመረጡ ሲሆኑ፣

አቶ ተሰማ ጋዲሴ ክልል 4 206 ድምፅ

አቶ ሰይድ ሬድዋን ከደቡብ ኢት/ ሕዝቦች ክልል 124 ድምፅ

አቶ ዘለሌ ፀጋሥላሴ ክልል 14 32 ድምፅ

በማግኘታቸው ሳይመረጡ ቀርተዋል ፡፡

9. የሕገ መንግሥት ትርጉም ኮሚቴ

የሕገ መንግሥት ትርጉም ኮሚቴ አባላት ተቆጣ ተሳትፎ የጉባኤን አባላት 1/3ኛ የድጋፍ ድምፅ አግኝተው ከተመዘገቡት 13 ዕጩዎች መካከል ፤

1. አቶ ሙሉጌታ አመና ክልል 4 /ብሔረሰብ ኦሮሞ/ 488 ድምፅ በማግኘት 1ኛ
2. አቶ መሐመድ ቢን መሐመድ ክልል 3 /ብሔረሰብ አርጎባ/ 459 ድምፅ በማግኘት 2ኛ
3. አቶ አብዱላሂ ኢብራሂም ክልል 5 /ብሔረሰብ ሶማሌ/ 457 ድምፅ በማግኘት 3ኛ
4. አቶ ሰለሞን አበበ ክልል 4 /ብሔረሰብ ኦሮሞ/ 456 ድምፅ በማግኘት 4ኛ
5. አቶ አለባቸው አባተ ክልል 3 /ብሔረሰብ አማራ/ 455 ድምፅ በማግኘት 5ኛ
6. አቶ ሰለሞን ሴታ ከደቡብ ኢት/ ሕዝቦች ክልል /ብሔረሰብ ወላይታ/ 448 ድምፅ በማግኘት 6ኛ
7. ወ/ት ዓለሚቱ ፋንቱ ክልል 3 /ብሔረሰብ አማራ/ 447 ድምፅ በማግኘት 7ኛ
8. አቶ ሰይድ ሬድዋን ከደቡብ ኢት/ ሕዝቦች ክልል /ብሔረሰብ ስልጤ/ 445 ድምፅ በማግኘት 8ኛ
9. አቶ ቱፋ ዳይቻ ከደቡብ ኢት/ ሕዝቦች ክልል /ብሔረሰብ ሲዳማ/ 436 ድምፅ በማግኘት 9ኛ
10. መ/ር ገ/ኪዳን አባይ ክልል 3 /ብሔረሰብ ትግራይ/ 436 ድምፅ በማግኘት 9ኛ

በማግኘት የሕገ መንግሥት ቅርፅ ኮሚቴ አባላት ሆነው ሲመረጡ ፤



1. አቶ ዊያም አማሀያ ክልል 6 185 ድምፅ
2. አቶ ሀሰን ሙሐመድ አብሴ ክልል 4 112 ድምፅ
3. አቶ ኑሪ ሙሳ ከደቡብ ኢት/ ሕዝቦች ክልል 71 ድምፅ

በማግኘታቸው ሳይመረጡ ቀርተዋል ፡፡

10 የሴቶች ጉዳይ ኮሚቴ

በመጨረሻም የሴቶች ጉዳይ ኮሚቴ አባላት ጥቆማ ተሳትፎ የጉባኤን አባላት 1/3ኛ የድጋፍ ድምፅ አግኝተው በዕጩነት ከተመዘገቡት 13 አባላት መካከል ፤

1. ዶ/ር ሃና ተመስገን ክልል 4 /ብሔሰብ ኦሮሚያ/ 486 ድምፅ በማግኘት 1ኛ
2. ወ/ሮ ብሩር መሐመድ ክልል 1 /ብሔሰብ ትግራይ/ 486 ድምፅ በማግኘት 2ኛ
3. ወ/ሮ ባጋለች ደምሴ ክልል 4 /ብሔሰብ ኦሮሚያ/ 462 ድምፅ በማግኘት 3ኛ
4. ወ/ሮ ፅጌ አሰፋው ክልል 3 /ብሔሰብ አማራ/ 460 ድምፅ በማግኘት 4ኛ
5. ወ/ሮ ዓለምፀሐይ ምህረተአብ ክልል 1 /ብሔሰብ ትግራይ/ 421 ድምፅ በማግኘት 5ኛ
6. ወ/ሮ ራሀመት ዩሱፍ ክልል 3 /ብሔሰብ አማራ/ 414 ድምፅ በማግኘት 6ኛ
7. ወ/ሮ አለማሽ ግርማይ ክልል 1 /ብሔሰብ ትግራይ/ 391 ድምፅ በማግኘት 7ኛ
8. ወ/ሮ በለጡ ኢዶኤ ክልል 14 /ብሔሰብ ኦሮሞ/ 382 ድምፅ በማግኘት 8ኛ
9. ወ/ሮ አለምሸት ይጥኑ ክልል 3 /ብሔሰብ አማራ/ 376 ድምፅ በማግኘት 9ኛ
10. ወ/ሮ ፋጤ መሐመድ ክልል 4 /ብሔሰብ ኦሮሚያ/ 360 ድምፅ በማግኘት 10ኛ

በማግኘት የሴቶች ጉዳይ ኮሚቴ አባላት ሆነው ሲመረጡ

1. አቶ ተስማ ጋዲሳ ከክልል 4 — 349 ድምፅ
2. ወ/ሮ አይሻ ዑመር ከክልል 4 — 181 ድምፅ
3. ወ/ሮ ደስታ አስፋ ከክልል 14 — 146 ድምፅ

በማግኘታቸው ሳይመረጡ ቀርተዋል ።

በመቀጠልም የጉባኤው ሊቀመንበር ጉባኤው ከሰዓት በኋላ ፣

1. የጉባኤውን ቃለጉባኤ ቁጥር አንድ እና ሁለት ማፅደቅ ፣
2. የጉባኤውን ውስጠ ደንብ ማፅደቅ ፣

የሚሉ አጀንዳዎች ላይ ውይይት እንደሚደረግ ገልጸው ጉባኤው ከቀኑ 6:55 ሰዓት ለምሳ ተነስቷል ።

ጉባኤው ከሰዓት በኋላ በ9:10 ሰዓት የጉባኤው ቃለጉባኤ ቁጥር አንድ ላይ ውይይት ጀምሯል ።

በዚህም መሠረት በቅድሚያ ሊቀመንበሩ ቃለጉባኤ ቁጥር 1 ላይ ያልተካተተ ሀሳብ ሆነ አስተያየት ካላቸው ማቅረብ እንደሚችሉ ባሳሰቡት መሠረት ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል አቶ ዓለሙ ፍቼ ቃለጉባኤው ጉባኤው የተመለከታቸውና የተነጋገረባቸው ቁምነገሮች እንዲሁም ያከናወናቸውን ድርጊቶች ነጥብ በነጥብ ያስቀመጠ ቢሆንም ጉባኤው በይፋ የተከፈተው ከሰዓት በፊት ስለሆነ በቃለጉባኤው ገጽ 1 ላይ "... ከሰዓት በኋላ የተጀመረው የኢትዮጵያ ሕገ መንግሥት ጉባኤ... " የሚለው ከሰዓት በፊት ተብሎ እንዲስተካከልና ለታሪካዊነቱም ጉባኤው የተጀመረበት ሰዓት እንዲሁም በጉባኤው የሚገኙትን ለማረጋገጥ የተወካዮች ስም ዝርዝር ከነተወከሉበት ክልል በቃለጉባኤው መግቢያ ላይ እንዲካተቱ ፣ በጉባኤው መክፈቻ ወቅት በክቡር ፕሬዚዳንት መለስ ዜናዊ ፣ በአቶ ከማል በድሪና በአቶ ክፍሌ ወዳጆ የተደረጉት ታሪካዊ ንግግሮች ደግሞ በአባሪነት ወይም በመግቢያነት እንዲገቡ ጠይቀዋል ።

ሊቀመንበሩ በሰጡት ምላሽ በጉባኤው መክፈቻ ወቅት የተደረጉ ንግግሮችና በጉባኤው ላይ የተገኙ አባላት ስም ዝርዝር እንደ አባሪ ሊሆን እንደሚችል ጠቁመው ለወደፊቱም ቢሆን በእያንዳንዱ ስብሰባ የተሳታፊዎች ስም ዝርዝር ከቃለጉባኤው ጋር ተያይዞ መግባት እንዳለበት አመልክተዋል ።

በተጨማሪም ጧት የጉባኤው መክፈቻ ሥነ ሥርዓት ቢከናወንም ዝግጅቱም ሆነ ውይይቱ / ንግግሩ / በጉባኤው ሳይሆን ከምርጫ ቦርድና ከሕገ መንግሥት ኮሚሽን እንደነበር ፣ ጉባኤው በራሱ አመራር ውይይቱን የጀመረው ከሰዓት በኋላ መሆኑን ፣ ሆኖም የጉባኤው መክፈቻ ሥነ ሥርዓት ራሱን ችሎ እንደሚሠራ በዚሁም የአባላት ስም ዝርዝር እንደሚገባና ከሌሎች ቃለጉባኤዎች ጋር እንደሚጠረዝ ከቃለጉባኤ ፀሐፊዎች አስተያየት እንደተሰነዘረ ጠቅሰዋል ።



አያይዘውም ሌላ በቃለጉባኤ ቁጥር 1 ላይ ያልተካተተ ሀሳብ አለ የሚል ሀሳብ ካለ እንዲቀርብ በጠየቁት መሠረት ፣ በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ውስጥ የተካተተውን የሕገ መንግሥት ጉባኤው መርምሮና ተመልክቶ ማዳበርም ሆነ ማስተካከል እንደሚችል ፕሬዚዳንት መለስ ዜናዊ ለጉባኤው ባስተላለፉት መልዕክት መሠረት ጉባኤው በእያንዳንዱ ጉዳይ ላይ ተከራክሮ ፈር ማስያዝ እንዳለበት ከክልል 14 አቶ ታሪኩ ገልጸው እንደነበር ሆኖም ከእርሳቸው ቀድመውና በኋላ ከተናገሩት ሰዎች ቅደም ተከተል አኳያ ሲመለከቱት ሀሳባቸው በቃለጉባኤው እንዳልተካተተ አስታውቀዋል ።

ከክልል 4 አቶ ሁሴን መሐመድ ጊዜያዊ ኮሚቴው ተገቢውን አመራር ስለሰጠ ለወደፊቱም በዚሁ ቢቀጥል ተገቢ አመራር እንደሚሰጥ በማመን በቋሚነት እንዲያገለግል ለቤቱ ጥያቄ አቅርበው እንደነበር በማስታወስ በቃለጉባኤው ገጽ 10 ላይ ግን ጊዜያዊ ኮሚቴው አስመራጭ ኮሚቴ ሆኖ እንደገና እንዲሠራ እዳሉ ተደርጎ ስለተጠቀሰ ያልተናገሩት እንደሠፈረ አመልክተው እንዲስተካከል ጠይቀዋል ።

ከክልል 14 ደግሞ አቶ አሊ አብዶ በቃለጉባኤው ገጽ 8 ፓራግራፍ 2 በአራተኛው መሥመር ላይ "...የየቀበሌዎቹ ኗሪዎች ቁጥር የተለያየ ሲሆን ..." የሚለው ከተናገሩት ሀሳብ ጋር እንደማይሄድ እና ሕዝቡ በውይይቱ ወቅት ተወካዮች በየአንቀጹ እንዲነጋገሩበት መርጧል የሚል ሀሳብ የነበራቸው ሲሆን በ7ኛ መሥመር ላይ ግን "... ሕዝቡ በአንድ ቀን ውስጥ ሀሳቡን መግለጹንና በዚህም ወቅት አወያዮች እንደነበሩት ..." ስለሚል በድምፅ ከተቀረጸው ታይቶ እንዲስተካከል ሀሳብ አቅርበዋል ።

በማስከተልም በቃለጉባኤ ቁጥር 2 ላይ ውይይቱ ቀጥሎ ፣ ከክልል 5 አቶ መሀሙድ ድሪር በቃለጉባኤው ገጽ 9 ላይ ስማቸው አቶ አህመድ ድራራ ስለተባለ እንዲስተካከል ፣ እንዲሁም በሌላው ቃለጉባኤ ላይ የክልላቸው ስም ሳይጠቀስ የታለፈበት ሁኔታ ስላለ ክልል 5 ተብሎ ተብሎ እንዲጻፍ አመልክተዋል ።

ከክልል 14 አቶ መኩሪያ ቦሬሳ በቃለጉባኤው ገጽ 4 ፓራግራፍ 14ኛው መሥመር ላይ አቶ መኩሪያ ቦሬሳ የተባለው ትክክለኛ በሆነ መልኩ ስማቸው እንደሚቀመጥለትና የቀረበውንም ሀሳብ እርሳቸው እንዳልተናገሩት ጠቅሰው በሌላ ሰው ሀሳቡን የገለጹት ከክልል 14 አቶ ቶሌራ ዐዲ መሆናቸውን ጠቅሰው እንዲስተካከል ጠይቀዋል ።

ቃለጉባኤው ገጽ 1 ላይ ጥቅምት 19 ቀን 1987 ዓ.ም ጉባኤው እንዲቀጥል በሚጠቀሰው ላይ ከሰዓት በኋላ መሆኑንና የተጀመረበትን ሰዓት እንዲያካትት ሀሳብ ከቤቱ ቀርቧል ።

አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 በስብሰባው ወቅት ያቀረቡት ሀሳብ በቀደሚያ የኮሚቴዎችን አስፈላጊነት እንዲያስረዱ ፣ አወቃቀሩም አባላቶችን ግምት ውስጥ ያስገባ እንዲሆን በመሠረቱ ሀሳቡ እንደሚደገፈው ፣ ሰነዱን መሠረት በማድረግ ምን ዓይነትና ምን ያህል ኮሚቴዎች የሚለው ሰነዱን ካየን በኋላ እሱን መሠረት በማድረግ ቢወሰን ይሻላል የሚል እንደነበር ከክልል 3 አቶ አዲሱ ለገሠ አስታውሰው በቃለጉባኤው ገጽ 2 ፓራግራፍ 2 ላይ የሠፈረው ግን መሠረተ ሀሳቡን እንዳላካተተ ገልጸዋል ።

ከክልል 14 አቶ ጇምበሬ ገ/መድህን በቃለጉባኤው ገጽ 5 ላይ ከደቡብ የኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል እንደተወከሉ የሚጠቀሰው ስህተት ስለሆነ እንዲስተካከል ጠይቀዋል ።

ከክልል 1 አቶ አባይ ፀሐዬ ያቀረቡት አስታራቂ ሀሳብ ተመራጮች እርስ በርስ ተወዳድረው ለቤቱ ያቀረቡቱና በኋላ ቤቱ ይቀበለው ወይም ያስተካክላል የሚል እንጂ በቃለጉባኤው ገጽ 4 ፓራግራፍ 2 በመሥመር 3 እና 4 ላይ ድጋፍ ባለመልኩ እንደተቀመጠው በኋላ ይወሰን የሚል ባለመሆኑ እንዲስተካከል አሳስበዋል።

ከክልል 4 አቶ አሰፋው ቀኖ በቃለጉባኤው ገጽ 5 የመጀመሪያው መሥመር ላይ የተጠቀሰው ሀሳብ የተናገሩት አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ የተናገሩትን ሙሉ በሙሉ እንደሚደግፉ ፣ በተጨማሪም የሕገ መንግሥቱን ረቂቅ ለማፅደቅ በ3 ሰዎች ብቻ ስለማይበቃ የኮሚቴው አባላት አብረው እንዲሠሩ የሚል እንደነበር አስታውቀው ይህ ግን በቃለጉባኤው በትክክል ስላልተቀመጠ እንዲስተካከል ጠይቀዋል ።

በቃለጉባኤ 1 እና 2 ላይ ከላይ የተዘረዘሩት የማስተካከያ ሀሳቦች በድምፅ ከተቀረጸው ተመሳክሮ መስተካከል እንዳለባቸው ቤቱ ተቀብሎታል ።



ከዚያም እያንዳንዱ የጉባኤው አባል የተናገረውን ሁሉ ነገር ሳይቀር ቃል በቃል ከቴፕ ካልተገለበጠ በስተቀር በቃለጉባኤው ውስጥ ማስቀመጥ አስቸጋሪ ስለሚሆን በጣም መሠረታዊ የሆኑ ነጥቦችን ሳይለቁ እንዲሁም ሳይቀይሩ መጻፍ እንደሚያስፈልግና ጉባኤው መሠረታዊ ነጥቦችን ማረጋገጥ እንጂ በየቃላት ጉዳዮች ላይ ማትኮር እንደማያስፈልግ በተለያዩ የጉባኤ አባላት ተገልጿል ።

ቀጥሎም ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል አቶ ቃደሰ ዓለማየሁ በስብሰባ ወቅት የተናገሩት ቃል በቃለጉባኤ መካተቱን መረጋገጥ እንጂ የተናገሩት ቃል በቃለጉባኤው ሰፍሮ ሲቀርብ ፀያፍ መስሎ ከታየ ያልተናገርኩት ነው ማለት እንደማይገባ አሳስበዋል ።

ሊቀመንበሩ በበኩላቸው የጉባኤው ውይይት የሚያዘው በጽሑፍ ብቻ ሳይሆን በቴፕም ጭምር ስለሚቀረጽ አንድ ሰው የተናገረውን አልተናገርኩም ብሎ ሊክድ እንደማይችል ምላሽ ሰጥተዋል ።

በማስከተልም በጉባኤው ቃለጉባኤ ቁጥር 1 እና 2 ላይ አንዳንድ ስህተቶች እንዳሉና እነዚህ ስህተቶች ወደፊት እንዳይደገሙ በውይይቱ ወቅት ግለሰቦች የተናገሩት ከመጻፉና ከማባዛቱ በፊት ረቂቁ ለተናገሩ ሰዎች ቀርቦ የተናገሩትን ሙሉ ቃልና ሀሳባቸውን የሚገልጽ መሆኑን አስተያየት ተጠይቀው እንዲያረጋግጡ እንዲደረግ በአንድ የጉባኤው አባል ሀሳብ ቀርቧል ።

ሌላው የጉባኤው አባልም የቀረበውን ሀሳብ በመደገፍ የጉባኤ አባላት ሂደው ረቂቁን በማየት ሳይሆን ቃለጉባኤ ፀሐፊዎች ካረቀቁ በኋላ ጉባኤው ሥራ ከመጀመሩ በፊት ረቂቁ ለጉባኤው እንዲነበብና ሀሳቡ ያልተስተካከለለት አባል ተነስቶ በአጭሩ ለጉባኤው እንዲያስረዳ ቢደረግ ጊዜም እንደሚቆጥብ አስተያየት ሰንዝረዋል ።

በዚህም ወቅት የጉባኤው ሊቀመንበር እያንዳንዱ የጉባኤ አባል የሚናገረው በጉባኤው ስብሰባ አዳራሽ ሁሉም አባላት እየሰሙ ስለሆነ የተናገረው ቃል በትክክል በቃለጉባኤ ካልተካተተም በጉባኤተኛው ፊት ማስተካከል እንጂ እያንዳንዱ የጉባኤ አባል ቃለጉባኤ ፀሐፊዎች ዘንድ በመሄድ ይህ ያስተካክሉልኝ ቢል ትክክለኛ አሠራር እንዳልሆነ አስገንዝበዋል ።

በማያያዝም የጉባኤው ዋና ፀሐፊ ጉባኤው ቃለጉባኤን በተመለከተ ዋናው ተግባር በአባላት የሚነሱ መሠረተ ሀሳብ ሳይዛባ መያዙን ማረጋገጥ ሲሆን በቃለጉባኤነት የተያዘውን ሰነድ ተናጋሪው በግል ማረጋገጡ ከጥቅሙ ይልቅ ጉዳቱ እንደሚያይል ዲሞክራሲያዊ ባህሪውን እንደሚያሳጣው ፣ ስለዚህ በቃለጉባኤነት የተያዘውን ረቂቅ ለማንበብ አጭር ጊዜ እንደሚወስድ በጉባኤው ፊት ተነስ መታረም የሚገባቸው ጉዳዮች በያሉ ታርመው በሰነድነት መያዝ እንዳለበት ፣

የሚቀርቡ
ስሁተት ካለም የጉባኤው አባላትና በተለያየ መንገድ በጉባኤው ውስጥ ቃለጉባኤን
ሰዶች ማመሳከሪያ እንደሚሆን ፣ ለወደፊቱም በጉባኤው ውስጠ ደንብ
ማን እንደሚከታተል ለማገለጽ በሚዜው ክትትል ተደርጎ መታረም የሚገባው
ታርሞ ለጉባኤው እንደሚቀርብ አብራርተዋል ።

አስለውም ቃለጉባኤ ያዥዎች እንወቅ የግል ሀሳብ ወደጋል ስለተቀመጡ
የአወጣዎውን የጉባኤ አባላት ድምፅ ቢሰሙም በአንዳንድ ቦታ ላይ ችግር ስላለ ቦታ
ይሰማቸው የግል ተቆማና እንዳንድ ጥያቄዎች ሲነሱ ቃለጉኤውን በምን ሁኔታ
እንደያዙት የማብራሪት ዕድል ቢሰማቸው የግል አስተያየት ወይ መድረኩ
እንደቀርብ ጠቅሰው ጉባኤው ውስጠ ደንቡን አስከሚያረቅ ድረስ ቃለጉባኤ
ያዥዎችም ሆነ ሌላውን ሥራ የሚያከናውኑ ሠራተኞች ቀደም ብሎ ተዘጋጅቶላቸው
በቆየው መልኩ እንዲቀጥሉ ለወደፊቱም ቃለጉባኤ ያዥዎች ይቀጥሉ ወይስ
ይለወጡ የሚለው በኋላ ሊታይ እንደሚችል ፣ ሆኖም ለጊዜው ስማቸውንና
ብዛታቸውን መግለጽ ጠቃሚ እንደሚሆን ጠቁመው ስማቸውን በመዘርዘር
ቁጥራቸው 7 እንደሆነ አስታውቀው የጉባኤ አባላትን ንግግር በሚገባ ለመስማት
የሚችሉበት ቦታ እንደሚዘጋጅላቸው አመልክተዋል ።

በመጨረሻም ቃለጉባኤ ቁጥር 1 እና 2 ከማሻሻያዎቻቸው ጋር ለማፅደቅ
ለድምፅ ቀረበው ቤቱ በሙሉ ድምፅ አፅድቋቸዋል ።

ቀጥሎም በጉባኤው ውስጠ ደንብ ላይ ውይይት የተጀመረ ሲሆን በቅድሚያ
ሊቀመንበሩ ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ውስጠ ደንቡን በጉባኤው ዕረፍት ጊዜ ስለታደለ
አብዛኛው አባል እንዳገኘ በመጥቀስ በቅድሚያ ስለአዘጋጀጀቱ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ
አቶ አዲሱ ለገሠ ማብራሪያ ከሰጡ በኋላ ጉባኤው በክፍል በክፍል ቢመለከተው
እንደሚሻል አስተያየት አቅርበዋል ።

በዚህም መሠረት በመድረኩ ላይ ባለው የከሰዓት በኋላው ስብሰባ የተገኙ አባላት
ብዛት 524 መሆኑና ቢሕገ መንግሥት አዘጋጅ ኮሚቴ የቀረበው ሰነድ ግን የጉባኤው
አባላት ቁጥር 541 እንደሆነ ስለሚያመለክት ከኮሚቴው ጋር በመነጋገር የአባላቱ
ብዛት እንደሚስተካከል አቶ አዲሱ ለገሠ ጠቁመው የጉባኤው አመራር አባላት
ውስጠ ደንብ እንዲያዘጋጅ ቀደም ሲል በተቀበሉት ውክልና መሠረት የሕገ
መንግሥት ኮሚሽን ያዘጋጀውን ረቂቅ መሸ ሀሳብና ከሌሎች ሰዶችን ጋር
በማዛመድ ረቂቅ ውስጠ ደንብ ለማቅረብ እንደተሞከረ በመጥቀስ ውስጠ ደንቡን
ለቤቱ በንባብ አሰምተው ጉባኤው ለሻይ ዕረፍት ተነስቷል ።

ከሻይ ዕረፍት በኋላም ሊቀመንበሩ ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ጉባኤው ውስጠ ደንቡን
አንቀጽ በአንቀጽ በመመልከት ውይይቱ እንደሚያካሄድ ገልፀው በአንቀጽ አንድ
ላይ አስተያየት ካለ እንዲቀርብ አሳስበዋል ።



በዚህም መሠረት ከክልል 5 አቶ መሀሙድ ድሪር በአንቀጽ አንድ ንዑስ አንቀጽ
ላይ በጉባኤው ውስጥ በአባልነት መሳተፍ የሚችሉ 548 እንደሆኑ ቢጠቀስም
የአባላት ቁጥር ያን ያህል እንዳልሆነ ገልጸዋል ።

በማያያዝም ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል አቶ ማትዮስ መርከቡ የጉባኤው
አመራር አካል የጉባኤውን ውስጠ ደንብ እንዲያዘጋጅ ኃላፊነት ሲሰጠው የጉባኤው
አባላት አቀማመጥም እንደያስማቸው ቅድም ተከተል እንዲሆን ተብሎ እንደነበር
አስታውሰው ለቁጥጥር እንዲያመችና ጉባኤተኛው እርስ በርስ እንዲተዋወቅ
ለማድረግ ሲባል ጉባኤው ካመሰበት አቀማመጡ በአማርኛ ፊደል ቅድም ተከተል
ቢስተካከል እንደሚሻል ሀሳብ አቅርበዋል ።

ለተነሱት ሀሳቦች ከአመራሩ በተሰጠው ምላሽ የጉባኤው አባላት ቁጥርን
በተመለከተ ከምርጫ ኮሚሽን የተገኘው ሰነድ ከ548 ስለሚያንስ ሰነዱ ከታተመ
በኋላ ምርጫ ተካሂዶ ከሆነ እንዲጣራ ጉባኤው በቅድሚያ ከአንቀጽ 1 ርዕስ ጀምሮ
አንቀጹ ጥተታቸው ንዑስ አንቀጾች ላይ ከተወያየ በኋላ የተለየ ተጨማሪ ሀሳብ ካለ
ሊቀርብ እንደሚችል ተገልጿል ።

ከዚያም ከክልል 1 አቶ ሙሉጌታ ህሕይወት በምርጫ ኮሚሽን ተዘጋጅቶ
ጥቅምት 18 ቀን 1987 ዓ.ም ለጉባኤው በተሰጠው ሪፖርት ላይ በ543 የምርጫ
ጣቢያዎች ምርጫ ተካሂዶ 543 አባላት እንደተመረጡና በሌሎች 5 ወረዳዎች
ማለትም በክልል 6 ውስጥ 2 ወረዳዎች ፣ በክልል 6 እና 4 መካከል ደግሞ 3
ወረዳዎች በተለያዩ ምክንያቶች ምርጫ ያልተካሄደ መሆኑን ስለሚያሳይ የምርጫ
ቦርድ ሰብሳቢ ባቀረቡት ሪፖርት መሠረት በውስጠ ደንቡ አንቀጽ 1 ንዑስ አንቀጽ
1 ላይ በጉባኤው ውስጥ መሳተፍ የሚችሉት አባላት 548 እንደሆነ የሚያመለክተው
543 ተብሎ እንዲስተካከል እንዲሁም በጉባኤው መሳተፍ ሲባል ሀሳብ መስጠትና
መከራከርን ጨምሮ እስከ ድምፅ መስጠት ያሉትን የተለያዩ ደረጃዎች የሚያካትት
ሲሆን በአንቀጽ 1 ንዑስ አንቀጽ 2 ላይ ግን የጋዜጠኞች ፣ ጥሪ የተደረገላቸው
እንግዶችና ባለሙያዎች ተሳትፎ እንደ ጉባኤተኛ አለመሆኑን በግልጽ
እንደማያመለክት አስተያየት ሰጥተዋል ።

የጉባኤው ዋና ፀሐፊነት አዲሱ ለገሠ ለጉባኤው የተሰጠው የጉባኤውን አባላት
ስም ዝርዝር የያዘ ሰነድ የአባላት ብዛት 541 መሆኑን እንደሚያመለክት ፣ ሆኖም

በክልል 5 ውስጥ በ3 ወረዳዎች ማለትም በኤረር ፣ በአዋሬና ደጋሀቡር በአዲስ መልክ ምርጫ ስለተካሄደ 3 ተጨማሪ አባላት ስለተመረጡ ጠቅላላው የጉባኤ አባላት ቁጥር 544 እንደሚሆን ፣ ይሁን እንጂ የቀረቡት ሰነዶች የተለያየ የአባላት ቁጥር ስለሚያመለክት ቁጥሩን አረጋግጦ ማካተት እንደሚሻል ገልጸው አንቀጽ 1 ንዑስ አንቀጽ 2ን በተመለከተ እንደተጠቆመው ሁሉ ታዛቢውንና ተሰብሳቢውን /ጉባኤተኛውን/ የማይለይ ስለሆነ ለይቶ ለማመልከት እንዲቻል ንዑስ አንቀጹ "ከጉባኤው አባላት በተጨማሪ በጉባኤው ፈቃድ ስብሰባ ውስጥ በታዛቢነት የሚገቡ ጋዜጠኞች ፣ ጥሪ የተደረገላቸው እንግዶችና ባለሙያዎች ሊሳተፉ ይችላሉ" በሚል እንዲሻሻል ሀሳብ አቅርበዋል ።

በማስከተልም ከክልል 4 አቶ ግርማ ብሩ ክፍል 1 ስለጉባኤው አባላት ስለሚገልጽ በውስጡ የሚካተቱ አንቀጾችም ሆኑ ንዑሳን አንቀጾች ስለጉባኤው አባላት ማመልከት ስላለባቸው በአንቀጽ 1 ንዑስ አንቀጽ 2 ያለው " በጉባኤው ፈቃድ ስብሰባ ውስጥ የሚገቡ ጋዜጠኞች ፣ ጥሪ የተደረገላቸው እንግዶችና ባለሙያዎች በአድማጭነት ፣ በታዛቢነትና በአስረጅነት ሊሳተፉ ይችላሉ " በሚል ተሻሽሎ ስለጉባኤው አባላት *መሳተፍ ከሚገልጸው በስተመጨረሻ ለብቻው ተለይቶ እንዲቀመጥ* አስተያየት ሰንዝረዋል ።

ቀጥሎም ከክልል 14 አቶ አዳሙ ደገፋ ውስጠ ደንቡ ብዙ የሚሻሻሉ ነገሮች እንዳሉበት በመጥቀስ የጉባኤው አባላት ውስጠ ደንቡን ወስደው ለአንድ ቀን በማየት የማሻሻያ ሀሳብን ይዘው እንዲመጡ እንዲደረግ ሀሳብ አቅርበዋል ።

ሊቀመንበሩ ባለፈው የጉባኤው ስብሰባ የኮሚቴ አባላት ምርጫና ቃለጉባኤዎችን የማፅደቅ ሁኔታ ከተከናወነ በኋላ ውይይቱ በውስጠ ደንብ እንደሚሆን ተገልጸ ውስጠ ደንቡ በአጀንዳነት ተይዞ እንደቆየ ገልጸው በዚያን ወቅት በሥነ ሥርዓት ማስቆም ይቻል እንደነበረ ፣ በአሁኑ ሰዓት ግን በውስጠ ደንቡ ላይ ውይይቱ ተጀምሮ ሀሳብ ከተንሸራሸረ በኋላ እናንብበው ማለት ከሥነ ሥርዓት ውጭ እንደሆነ አስገንዝበዋል ።

በመቀጠልም ከክልል 14 አቶ አሊ አብዶ በጉባኤው የሚሳተፉትን በአንቀጽ 1 በተቀመጠው መንገድ አንድ ላይ ስብስቦ ማስቀመጡ የተሻለ ስለሆነና ክፍል 1 ግን በጉባኤው ስለመሳተፍ ብቻ ሳይሆን የመናገር ነፃነት ፣ ያለመታሰር መብት ፣ ከጉባኤው አባልነት ስለመሰረዝና የቅጣት ደረጃዎችን ስለሚያካትት የክፍሉ



አጠቃላይ ርዕስ የሆነው " ... ስለጉባኤ አባላት " የሚለው" ... ስለገቡኤው አባላትና ተሳታፊዎች " በሚል እንዲሻሻል ሀሳብ አቅርበዋል ።

እንዲሁም ከክልል 4 አቶ አህመዲን ኢብራሂም አንቀጽ 1 ንዑስ አንቀጽ 1 እና 3 በጉባኤው የሚሳተፉትን ሰዎች የሚመለከቱ እንደሆነ ፣ አንቀጽ 1 ንዑስ አንቀጽ 2 ግን "... በተጨማሪ ..." ስለሚል ከጉባኤ አባላት በተጨማሪ በልዩ ሁኔታ የሚገኙትን ለማለት ስለሆነ ንዑስ አንቀጽ 2 እና 3 ቦታቸው ቢዘዋወር ሊጣጣም እንደሚችል ጠቅሰዋል ።

ቀጥሎም ከክልል 4 አቶ አበራ ዮሴፍ አንቀጽ 1 ንዑስ አንቀጽ 1 እና 2 "እንዲሁም " በሚል አያያዥ ቃል ተጣምረው አንድ ንዑስ አንቀጽ ቢሆኑ እንደሚሻል አስተያየት ሰንዝረዋል ።

በማስከተልም ሊቀመንበሩ በተነሳው ሀሳብ ላይ ቤቱ ከተስማማበት ቋንቋውን የሕግ ባለሙያዎች ሊያስተካክሉት ስለሚችሉ በጉዳዩ ላይ ብዙ ጊዜ ማጥፋት እንደማያስፈልግ ገልጸዋል ።

ቀጥሎም ከክልል 4 አቶ ኩማ ደመቅሳ ቀደም ሲል አቶ አዲሱ ለገሠ ፣ አቶ አህመዲን ኢብራሂምና አቶ አሊ አብዶ ያቀረቡትን የማሻሻያ ሀሳብ እንደሚደግፉና ይህን መሠረት በማድረግ የሕግ ባለሙያዎች ሊያስተካክሉት እንደሚገባ ሀሳብ አቅርበዋል ።

በሌላ በኩልም ከክልል 14 ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ 20 የሚሻሻሉ ጉዳዮች እንዳሏቸውና አሁን በተያዘው መንገድ መቀጠሉ ብዙ ጊዜ ስለሚፈጅ ማንኛው ሰው ሊታረም ይገባል የሚለውን የማሻሻያ ሀሳብ በጽሑፍ አዘጋጅቶ ለኤክስፐርቶች ቢሰጥና ኤክስፐርቶች የሁሉንም ሀሳብ አጠናቅረው አሻሽለው ቢያቀርቡት እንደሚሻል አስተያየት ሰንዝረዋል ።

አንድ የጉባኤ አባል ደግሞ ጊዜን መቆጠብ አስፈላጊ ቢሆንም እያንዳንዱ የጉባኤው አባል የሕዝብን ውክልና ይዞ የመጣው በአንቀጾቹ ላይ ተነጋግሮ ይሆነኛል የሚለውን እንዲቀመጥለት በመሆኑ በፊት ለፊት ሀሳብ መለዋወጥ ፣ መቃወምና አስተሳሰቡን መግለጽ ሲችል በጽሑፍ ለኤክስፐርቶች ወይም ለሕግ ባለሙያዎች ማቅረቡ ሕጋዊና ትክክል እንደማይሆን ጠቁመዋል ።

ከዚያም ከክልል 4 አቶ ግርማ ብሩ አንቀጽ 1 ንዑስ አንቀጽ 2 ቦታው እንዲቀየር ቀደም ሲል ሀሳብ ያቀረቡት ለውስጠ ደንቡ አቀማመጥና ስለጉባኤው አባላት የተጠቀሱትን ለማየት የሚፈልግ ሰው በፍጥነት ለማግኘት እንዲችል በማለት እንጂ "... ጋዜጠኞች ፣ ጥሪ የተደረገላቸው እንግዶችና ባለሙያዎች በአድማጭነት፣

በታዛቢነትና በአስረጅነት ሊሳተፉ ይችላሉ". ከተባለ አሁን ካለበት ቦታ ወጥቶ ራሱን በቻለ አንቀጽ ባይቀመጥም የአቀማመጥ እንጂ የፅንሰ ሐሳብ ልዩነት ስለማያመጣ ሀሳባቸውን ለመሳብ እንደሚችሉ አስታውቀዋል ።

በሌላ በኩል ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል አቶ ደራቶ ዳራ እና ከክልል 5 አቶ መሀሙድ ድሪር የጉባኤ አባላት ከጋዜጠኞች ፣ ጥሪ ከተደረገላቸው እንግዶችና ባለሙያዎች የተለየ ተልዕኮና መብት ስለሌላቸው እያንዳንዳቸው የሚኖራቸው ተሳትፎ እንደሚለያይ ፣ አንቀጽ 1 ንዑስ አንቀጽ 2 ግን የጉባኤ አባላትና ሌሎች ተሳታፊዎችን ልዩነት በደንብ ስላላስቀመጠ ከክልል 4 አቶ ግርማ ብሩ ንዑስ አንቀጹ ...ጋዜጠኞች ፣ ጥሪ የተደረገላቸው እንግዶችና ባለሙያዎች በታዛቢነት፣ በአድማጭነትና በአስረጅነት ሊሳተፉ ይችላሉ ኝ በሚል አቅርበውት የነበረው ማሻሻያ ሀሳብ ጉዳዩን ግልጽ ስለሚያደርገውና በዚህ መልክ መቀመጥ ስላለበት አቶ ግርማ ብሩ ሀሳባቸውን ቢስቡትም አቋማቸውን አቶ ዳቶራ ዳራ እና አቶ መሀሙድ ድሪር እንደሚደግፉት ፣ ንዑስ አንቀጽ 2 እና 3 ግን ቅድም ተከተላቸው መዛወር እንደሚኖርበት ሀሳብ አቅርበዋል ። ይህንኑ ሀሳብ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል አቶ ለማ ለማጎ እንደሚደግፉት ገልጸዋል ።

ከዚያም አንድ የጉባኤው አባልና ከክልል 5 ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን እስከ አሁን ድረስ አንቀጽ 1 ንዑስ አንቀጽ 2ን በተመለከተ በተካሄደው ውይይት በተለያዩ ሰዎች የቀረበው ሀሳብ መሠረታዊ ልዩነት ስለሌለው ተቃራኒነት በሌለው ሀሳብ ላይ መከራከር እንደማያስፈልግ አስተያየት ያቀረቡ ሲሆን ሁለት የጉባኤው አባለት ደግሞ ንዑስ አንቀጹ አቶ አዲሱ ለገሠ ባቀረቡት ማሻሻያ መሠረት እንዲስተካከል ጠይቀዋል ።

በዚህ ወቅትም ሊቀመንበሩ አንቀጽ 1 ንዑስ አንቀጽ 2 ይዘት ላይ ሁሉም የጉባኤው አባላት ቢስማሙም ልዩነቱ ንዑስ አንቀጹ ሌላ ርዕስ ተዘጋጅቶለት ለብቻው ይሁን የሚልና አሁን ባለበት ላይ ሆኖ ተስተካክሎ ይቀመጥ በሚል ሀሳብ መካከል እንደሆነ አመልክተዋል ።

በማስከተልም ከክልል 3 አቶ ቴዎድሮስ ባካፋ የክፍል አንድ ርዕስ "ስለጉባኤው አባላት" ስለሚል የጉባኤው አባላትን ጉዳይ እንዲያስታውቅ መደረግ እንዳለበትና አንጽ 1 ንዑስ አንቀጽ 2 ግን አቶ ግርማ ብሩ እንደጠቆሙት አንድ ራሱን በቻለ ርዕስ መካተት እንዳለበት ፣ ወይም የክፍሉ ርዕስ "ስለ ጉባኤው አባላትና ሌሎች ተሳታፊዎች" በሚል ተሻሽሎ አንቀጽ 1 ንዑስ አንቀጽ 2 "...በሥራ ሀላፊነታቸው የተነሳ



የሚገኙ ጋዜጠኞች ፣ ታዛቢዎች ፣ አድማጮችና ጥሪ የተደረገላቸው እንግዶች ..."ተብሎ በግልጽ መቀመጥ እንደሚገባው አስተያየት ሰንዝረዋል ።

ከዚያም ሊቀመንበሩ አንቀጽ 1ን በተመለከተ የቀረቡ አማራጭ ሀሳቦች በንዑስ አንቀጽ 2 ላይ የቃላት ማስተካከያ ተደርጎበት ከንዑስ አንቀጽ 3 ጋር ቅደም ተከተሉ ይለወጥ የሚልና ንዑስ አንቀጽ 2 የተለየ ርዕስ ተዘጋጅቶለት ተለይቶ ለብቻው ይቀመጥ የሚል መሆኑንና በሁለቱም አማራጭ ላይ ቤቱ በበቂ ሁኔታ ስለተወያየ በድምፅ እንዲወሰን ጠይቀዋል ።

እያይዘውም የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ በጉባኤው ውስጥ የተከሰተው ልዩነት የይዘት ለውጥ ሳይሆን የቅርጽ ጉዳይ መሆኑንና በድምፅ አሰጣጥ ላይ ችግር እንዳይፈጠር የአንቀጹን ርዕስ በመለወጥ ወይም የጉባኤው አባላትንና የሌሎች በስብሰባው የሚገኙ ሰዎች ለየብቻ በማስቀመጥ ማስማማት ስለሚቻል ቤቱ ወደ ድምፅ ከመሄዱ በፊት መጠነኛ ውይይት እንዲካሄድ በማሳሰብ የክፍል 1 ርዕስ ከክልል 3 አቶ ቴዎድሮስ ባካፋ እንደጠቀሱት "ስለጉባኤው አባላትና ሌሎች ተሳታፊዎች " በሚል በማሻሻል ወይም " ስለጉባኤው አባላት" በሚል ርዕስ "ስለጉባኤው መሳተፍ" በሚለው ውስጥ ቀደም ሲል እንደተጠቀሰው ተሳትፎን ስለሚያመለክት በመጀመሪያ የጉባኤ አባላትን የሚመለከተውን ፣ ከዚያም ቀጥሎ በሌላ አንቀጽ ደግሞ የሌሎች ተሳታፊዎች መግለጽ እንደሚቻል ሀሳብ አቅርበዋል ።

በማስከተልም ከክልል 1 አቶ ሸዋት ገ/ክርስቶስ ክርክሩ ክፍት ሆኖ ሀሳብ ሊሰጥበት እንደሚገባ ጠቁመው እስከ አሁን ድረስ በአቶ ግርማ ብሩ የቀረበውን ሀሳብ ስህተት የሆነበት ሁኔታ እንዳልቀረበና አማራጩ ትክክል አይደለም የሚል ሀሳብ ካለ ጉዳዩ ሊቀርብ እንደሚገባ ፣ ሀሳቡን የሚደግፍ አስተያየት ብቻ የሚቀርብ ከሆነ ግን ወደ ድምፅ መስጠት መሄድ እንደሚሻል ገልጸዋል ።

በተጨማሪም አቶ ታሪኩ ዕጌ አቶ ግርማ ብሩና አቶ አህመዲን ኢብራሂም ያቀረቡት ሀሳብ ግልጽ ስለሆነ የቀረቡት አማራጮች ለድምፅ እንዲቀርቡ አሳስበዋል ።

በመጨረሻም ሊቀመንበሩ ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ የዕለቱ ጉባኤ መጠናቀቂያ ሰዓት ስለደረሰ በነገው ዕለት ውይይቱ እንደሚቀጥል አስታውቀው የዕለቱ ስብሰባ ከቀኑ 12:00 ሰዓት ተጠናቋል ።

ጥቅምት 24 ቀን 1987 ዓ.ም ከጧቱ በ3:00 ሰዓት በተጀመረውና በሕገ መንግሥት ጉባኤ አዳራሽ በተካሄደው የኢትዮጵያ ሕገ መንግሥት ጉባኤ 525 አባላት የተገኙ ሲሆን የተመራውም በጉባኤው ሊቀመንበር በዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ነው ::

በመጀመሪያ ሊቀመንበሩ ትናንት ጉባኤው በውጠ ደንቡ አንቀጽ 1 ላይ የጀመረውን ውይይት እንደሚቀጥል አሳስበው ውስጠ ደንቡ ጉባኤው በሥራ ላይ ለሚቆይባቸው ጊዜያት ብቻ የሚያገለግል በመሆኑ በጉዳዩ ላይ ብዙ ጊዜ ማጥፋት እንደሌለበት ገልጸዋል ::

አያይዘውም አንቀጽ 1 ንዑስ አንቀጽ 2ን በተመለከተ የተወሰኑ ቃላት ተጨምረውበት እንዳለ ይቀመጥ የሚልና ከተቀመጠበት አንቀጽ ወጥቶ ለብቻው ይቀመጥ የሚሉ ሀሳቦች ቀርበው እንደነበር ጠቁመው ይህንኑ ጉዳይ በተመለከተ ንዑስ አንቀጹ ስለ ሌሎች ተሳታፊዎች የሚያወሳ በመሆኑና የነዚህ ወገኖች መብትና ግዴታ ከጉባኤው አባላት የተለየ በመሆኑ ንዑስ አንቀጹ አሁን ካለበት ወጥቶ አንቀጽ 6 ሆኖ ቢገባ የተሻለ ይሆናል የሚል ሀሳብ ያቀረቡ መሆኑን ገልጸው ቤቱ በጉዳዩ ላይ አስተያየት እንዲሰጥበት ጠይቀዋል ::

በአንድ በኩል ንዑስ አንቀጹ አንቀጽ 6 ሆኖ ከሚቀመጥ ሌሌች በስብሰባው ስለሚካፈሉ ሰዎች ተብሎ ባለበት እንዲሆን ከክልል 5 በአቶ መሀሙድ ድሪር ፣ ከክልል 3 በአቶ አቡኔ መንገሻ ሀሳብ ሲቀርብ በሌላ በኩል ደግሞ ቁምነገሩ የጉባኤ አባላቱን ሚና ከሌሎች ተሳታፊዎች መለየት በመሆኑ ከመድረኩ የቀረበው ሀሳብ በቂ ነው የሚል ሀሳብ ከክልል 1 በአቶ ተስፋይ ሐጎስ እና ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል በአቶ ታደሰ ግርሚሶ ቀርቧል ::

ከዚያም ከተለያዩ የጉባኤው አባላት ከመድረኩ በቀረበው ሀሳብ መሠረት ንዑስ አንቀጹ የቃላት መሻሻል ተደርጎበት ባለበት ይቀመጥ የሚል ሀሳብ ቀርቧል ::

በመቀጠልም በጉዳዩ ላይ በበቂ ሁኔታ ውይይት እንደተደረገበት ተገልጾ ውይይቱ ቆሞ በቀረቡት ሁለት ሀሳቦች ላይ ድምጽ እንዲሰጥ በመወሰኑ ፣

--አንቀጽ 1 ንዑስ አንቀጽ 2 የቃላት ማሻሻያ ተደርጎበት ባለበት ይሁን የሚለውን በመደገፍ 128 ፣

--ንዑስ አንቀጹ ተሻሽሎ አንቀጽ 6 ሆኖ ለብቻው ይቀመጥ የሚለውን በመደገፍ 398 ፣

--ድምፀ ተአቅቦ 4

ድምፅ በመመዝገቡ ንዑስ አንቀጹ ተሻሽሎ አንቀጽ 6 ሆኖ እንዲገባ ተወስኗል ::



በዚሁ መሠረት በክፍል አንድ ባሉ ሌሎች አንቀጾች ላይ አስተያየት ካለ ተጠይቆ በቅድሚያ በአንቀጽ 5 ንዑስ አንቀጽ 2/ሐ/ ላይ የተቀመጠውን የይግባኝ ጉዳይን በተመለከተ አንድ የጉባኤው አባል በጉባኤው ውሳኔ ከተሰናበተ በኋላ ይግባኝ የሚያሳማው ለየትኛው አካል ነው የሚል ጥያቄ አንድ የጉባኤ አባል አቅርበው ከዚህ ጉባኤ በላይ ይግባኝ ሰሚ አካል ባለመኖሩ ንዑስ አንቀጹ የዲስፕሊን እርምጃ የተወሰደበት ማንኛው አባል በ /ሀ/ እና በ /ለ/ የተቀመጡትን ቅጣቶች በተመለከተ ማስረጃውን በማያዝ ለጉባኤው ይግባኝ ማቅረብ ይችላል በሚል ሊሻሻል እንደሚችል አቶ አዲሱ ለገሠ ገልጸዋል ::

የተደረገው ማሻሻያ ተገቢ ቢሆንም እያንዳንዱ ማስጠንቀቂያ የደረሰው አባል ማስረጃ ስላለኝ ማስጠንቀቂያ የተሰጠኝ በስህተት ነው ይታይልኝ እያለ የጉባኤውን ሂደት እንዳያጓትተው ጉዳዩ በአጀንዳ ተይዞ ሊታይ የሚችለው የተወሰነ ድጋፍ ያገኘ እንደሆነ ብቻ መሆኑ መቀመጥ አለበት ሲሉ ከክልል 1 አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ሀሳብ አቅርበዋል ::

ጉዳዩን ለማየት 1/3ኛ የድጋፍ ድምፅ ያስፈልጋል የሚል ቢታከልበት ጉዳት እንደሌለው አቶ አዲሱ ለገሠ ገልጸው ይኸው ሀሳብ ከክልል 3 በአቶ ታደሰ ካሳ የተደገፈ ቢሆንም ጉባኤው ራሱን የቻለ የአጀንዳ አቀራረብ ሥርዓት ስላለው አጀንዳን በተመለለተ ምንም ተጨማሪ ነገር አያስፈልገውም የሚል ከክልል 5 በአቶ ሽምሰዲን አህመድ ቀርቧል ::

በዚሁ አንቀጽ 1/ሐ/ የተቀመጠው ዲስፕሊን ኮሚቴው አንድን አባል ለተወሰነ ጊዜ የማገድ ሥልጣን እንዳለው ተደርጎ የቀረበ ስለሆነ የዲስፕሊን ኮሚቴው ሥልጣኑ እስከምን ድረስ እንደሆነ እንዲብራራ ከክልል 3 አቶ ታደሰ ካሳ ጠይቀው በተሰጠው ማብራሪያ የጉባኤው አባላት የሕዝብ ተወካዮች በመሆናቸው የጉባኤ አባልነት መብትም እንደቀላል መታየት እንደሌለበት አንድ የጉባኤ አባል አስገንዝበዋል ::

አያይዘውም አቶ አዲሱ ለገሠ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ ጉባኤው ሳያውቀው ከስብሰባ ለአንድ ቀን እንኳን መታገድ የለበትም የሚል ግንዛቤ እንዳለና የዲስፕሊን ኮሚቴ ሥልጣንም የቃልና የፅሑፍ ማስጠንቀቂያ በመስጠት ብቻ መወሰን እንዳለበት ገልጸዋል ::

በሌላ በኩል አቶ አብዱራዛቅ መሐመድ ከክልል 14 በበኩላቸው አንድ አባል ጉባኤው ከተጀመረ በኋላ በጉባኤው ሂደት ላይ ችግር ቢፈጥር ጉዳዩ ወደ ዲስፕሊን ኮሚቴ ሳይሄድ ጉባኤው በሞሽን መልክ እርምጃ ሊወስድ ስለሚችል ይህ ጉዳይ መቀመጥ እንዳለበት ጠቁመው አንድ አባል የሚታገደውም ሆነ ከጉባኤው

የሚሰናበተው በጉባኤው 2/3ኛ ድምፅ ሲደገፍ ነው በሚል ቢቀመጥ የተሻለ ይሆናል የሚል ሀሳብ አቅርበዋል ።

በማያያዝም አቶ መኩሪያ ታፈሰ ከክልል 14 ጉባኤው አንድ አባል እንዴትና በምን ሁኔታ ከጉባኤው ይወገዳል ? የሚለውን ከማየቱ በፊት አንድ በሕዝብ የተወከለ የጉባኤ አባል በጉባኤው ውሳኔ ሊባረር ይችላልን ? የሚለውን መወሰን እንዳለበት ገልጸዋል ።

አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 ለሕዝብ ክብር ከመስጠት አኳያ ሲታይ ሕዝብ የወከለው የጉባኤ አባል በጉባኤው አባላት ውሳኔ መባረር የለበትም የሚለው ሀሳብ ትክክል መሆኑን ፣ በአንፃሩ ግን የአንድን አካባቢ ሕዝብ ተወካይ የተጣለበትን አደራ በመዘንጋት የሕዝቡን የወደፊት ዕድል ለመወሰን የተቀመጠ ጉባኤን ቢያውክና የጠቅላላ ሕዝቡን ክብር ወሳኝ ችግር ላይ የሚጥል ከሆነ ዝም ብሎ መመልከት አግባብ እንዳልሆነና በጉባኤው 2/3ኛ ድምፅ እንዲወገድ ማድረጉ በአንድ በኩል ጉባኤው ለሕዝብ ያለውን ከበሬታ ሲያሳይ በሌላ በኩል ደግሞ ውሳኔው ኃላፊነት በተሞላበት ሁኔታ መወሰኑን ያመለክታል የሚል ሀሳብ አቅርበዋል ።

ከዚያም በጉዳዩ ላይ የሚደረገው ውይይት በቂ በመሆኑ ይቁም የሚል ሀሳብ ቀርቦ ከ3 የተቃውሞና ከ6 ድምፀ ተአቅቦ በስተቀር አብዛኛው ደግፎታል ።

በዚህም መሠረት አንቀጽ 5 ንዑስ አንቀጽ 1/ሐ/ " ከጉባኤው አባላት ውስጥ ለተወሰነ ጊዜ የማገድ ወይም ባጠቃላይ ከጉባኤው መሰረዝን በተመለከተ በጉባኤው 2/3ኛ ድምፅ ሲደገፍ ይፈጸማል " በሚል ተሻሽሏል ።

የአንቀጽ 5/2/ የዲስፕሊን እርምጃ የተወሰደበት ማንኛውም አባል ማስረጃውን ለጉባኤው አቅርቦ በጉባኤው 1/3ኛ ድምፅ ሲደገፍ ይግባኙ ይታያል በሚል እንዲሻሻል 498 የድጋፍ 3 የተቃውሞና 6 የተአቅቦ ድምፅ ተመዝግቧል ። ቀጥሎም አንቀጽ 5/2/ ላይ በተደረገው ውይይት "የመናገር ነፃነት" የሚለው ርዕስ "ሀሳቡን የመግለጽ ነፃነት" በሚል ተስተካክሎ በአንቀጹ "ማንኛው የጉባኤ አባል በጉባኤው ሀሰቡን" ከሚለው ቀጥሎ "በቃልም ሆነ በፅሑፍ" የሚል ሐረግ እንዲታከልበት አቶ አህመድ ሰይድ ከክልል 3 ሀሳብ ያቀረቡ ሲሆን በሌላ በኩል ደግሞ ርዕሱ ብቻ ተስተካክሎ ሌላው እንዳለ ቢቀመጥ ተፈላጊውን መልዕክት ያስተላልፋል የሚል ሀሳብ ከበርካታ የጉባኤው አባላት ቀርቧል ።

በመቀጠልም የመናገር ነፃነት ለሁሉም ኢትዮጵያዊ የተፈቀደ በመሆኑ ጉባኤው እየተነጋገረ ያለው በኢሙኒቲ ጉዳይ ላይ ስለሆነ ርዕስ "ያለመከሰስ መብት" ተብሎ እንዲቀመጥ ከክልል 14 ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ አስተያየት ስለአቀረቡ ሊቀመንበሩ



የኢሙኒቲ ጉዳይን የሚያነሱ ሌሎች አንቀጾች እንዳሉ ገልጸው በዚሁ አንቀጽ እየታየ ያለው ሀሳቡን የመግለጽ ጉዳይ ብቻ መሆኑን አብራርተዋል ።

ከዚያም ርዕስ ብቻ ይሻሻል የሚለውና ርዕስ ተሻሽሎ በቀረበው የአንቀጹ ክፍል «በቃልም ሆነ በፅሑፍ» የሚል ሐረግ ይታከልበት የሚሉት ሁለት ሀሳቦች ለድምፅ ቀርቦ የመጀመሪያው 482 የድጋፍ አግኝቶ ሲያልፍ ሁለተኛው ደግሞ 9 ድምፅ በማግኘት ውድቅ ሆኗል ። 5 ድምፀ ተአቅቦም ተመዝግቧል ። በዚሁ ርዕስ ብቻ «ሀሳብን የመግለጽ» በሚል ተሻሽሎ አንቀጹ እንዳለ ፀድቋል ።

ከሻይ ዕረፍት በኋላ ውይይቱ በአንቀጽ 3 ላይ ቀጥሎ በተሰጠው አስተያየት ርዕሱ የጉባኤ አባላት ያለመታሰር መብት ተብሎ እንዲሻሻል አቶ ጉዲሳ ጃራ ከክልል 4 የጠየቁ ሲሆን በክፍል 1 ከቁጥር 1-5 ያሉት አንቀጾች የሚወሱት ስለጉባኤ አባላት ብቻ በመሆኑ ርዕስ እንዳለ ቢሆን እንደማያሻማ አቶ አዲሱ ለገሠ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አስረድተዋል ።

የአንቀጹ መነሻ ሀሳብ የሕዝብ እንደራሴን ማሰር ሕዝብን መቅጣት ስለሆነ አንድ የፓርላማ አባል የሆነ ሰው ከጉባኤ እንዳይሰናከል ለመከላከል መሆኑን ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 ገልጸው አንድ የጉባኤ አባል የሆነ ሰው ሳይታሰርም ተከሶ ፍርድ ቤት ወይም ፖሊስ ጣቢያ እንዲመላለስ በማድረግ ከጉባኤ እንዲሰናከል ማድረግ ስለሚቻል ርዕሱ "ያለመታሰር መብት " የሚል ሳይሆን " ያለመከሰስ መብት " በሚል መቀመጥ እንዳለበት አስገንዝበዋል ።

ይህንኑ ጉዳይ በተመለከተ አቶ አህመዲን ኢብራሂም ከክልል 4 በሰጡት ማብራሪያ ማንም ሰው ሊከሰስ እንደሚችል ፣ መሠረታዊው ጉዳይ ሰውዬው ተከሶ ምን ይሆናል? የሚለው መሆኑን አንድ የጉባኤ አባል ሆነ ሰው የጉባኤውን ሥራ ሳያጠናቅቅ ስለተከሰሰ ብቻ ፍርድ ቤት ወይም ፖሊስ ጣቢያ እንዳይመላለስ የሽውም የሕዝብ ተወካይ ሆኖ ጉባኤ ላይ በመሆኑ በቂ ምክንያት ስላለው ልዩ አስተያየት እንደሚሰጠው አብራርተው ከመከሰሱ ይልቅ አሳሳቢው መታሰሩ መሆኑን ገልጸዋል ።

አንቀጽ አንድ የጉባኤ አባል ከባድ ወንጀል ፈፅሞ እጅ ከፍንጅ ከተያዘና ጉባኤው ሲፈቅድ ሊታሰር እንደሚችል የሚያመለክት በመሆኑ አንድ የጉባኤ አባል በሁለት መንገዶች ሊታሰር ይችላል የሚል እንድምታ ስላለው ያለ ጉባኤው ፈቃድ የሚለው ሐረግ ጉባኤው አንድ አባል እንዲታሰር የሚፈቅድ ምን ምን ጉዳዮች ሲሟሉለት ነው ወደሚል ዝርዝር ጉዳይ ውስጥ ስለሚያስገባ ሐረጉ ቢወጣ የተሻለ ይሆናል የሚል ሀሳብ አቶ ሸምሰዲን አህመድ ከክልል 5 አቅርበዋል ።

ይህንኑ ጉዳይ በተመለከተ አቶ አዲሱ ለገሠ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ በሰጡት አስተያየት ከባድ ወንጀል የሚለው በሀገሪቱ በሚሠራበት የወንጀለኛ መቅጫ ሕግ

የተተረጎመ መሆኑን ፣ ዋናው ሀሳብ አንድ የጉባኤ አባል እጅ ከፍንጅ ወንጀል ሲሠራ ቢያዝ ሕጋዊ እርምጃውን የወሰደው አካል ጉዳዩን ለጉባኤው ማሳወቅ አለበት የሚል መሆኑን አስገንዝበው ሐረጉን በማውጣት ይህንኑ ሀሳብ የያዘ ዐረፍተ ነገር በአንቀጹ መጨረሻ ላይ ማከል እንደሚቻል አመልክተዋል ::

በሌላ በኩል ደግሞ አንድ የጉባኤ አባል ከባድ ወንጀል ሰርቶ እጅ ከፍንጅ ባይያዝም ፖሊስ ማስረጃ ይዞ በመቅረብ የጉባኤውን ፈቃድ ጠይቆ ሊያስረው የሚችልበት ሁኔታ ስላለ "ያለ ጉባኤው ፈቃድ" የሚለው መቀመጥ እንዳለበት አቶ አህመዲን ኢብራሂም ከክልል 4 ገልጸዋል ::

አንቀጹ ሲቀመጥ አንድ ወንጀል ፈጽሞ እጅ ከፍንጅ ሳይያዝ የቀረ የጉባኤ አባል በጉባኤው ጊዜ ለፈጸመው ወንጀል ሳይቀጣ እንዳይቀር እና የሕዝብ ተወካይ የሆነ አንድ ሰው ሕዝብ የሰጠው ኃላፊነት ስላለ ከጉባኤው እንዲቀር በሕግ አስፈጻሚ አካላት ጫና እንዳይደረግበት መከላከል የሚሉ ሁለት ፍላጎቶች እንዳሉና ሊጋጩ እንደሚችሉ አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 ገልጸው አንቀጹ ከፍተኛ ከለላ መስጠት ስላለበት እና የተፈጸመው ወንጀል ቀላል ነው ከባድ ነው ብሎ ሕግን የመተርጎም ሥልጣንም የሌላ አካል በመሆኑ "ያለ ጉባኤው ፈቃድ "የሚለው ቃል ቢወጣ እንደሚሻል አመልክተዋል ::

ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ ከክልል 1 በበኩላቸው አንቀጹ ሕጋዊ እርምጃ የወሰደ አካል ለጉባኤው ማሳወቅ አለበት የሚለውና ወንጀል ፈጽሞ እጅ ከፍንጅ ሳይያዝ የቀረን የጉባኤ አባል ለማሰር የጉባኤውን ፈቃድ ማግኘት አለበት የሚሉትን ሁለት ሀሳቦች ማንፀባረቅ እንዳለበት አሳስበዋል ::

"ያለ ጉባኤው ፈቃድ" የሚለው ሐረግ አፅንኦት ከመስጠት ሌላ አባሉ ተራ ሰው አለመሆኑን እንደሚያመለክት አቶ መሀመድ ድረር ከክልል 5 ገልጸው ሕጋዊ እርምጃ የወሰደ አካል ለቤቱ ማሳወቅ አለበት የሚለው ተገቢ እንደሆነ ጠቅሰዋል ::

መጨረሻም " ማንኛውም የጉባኤ አባል ከባድ ወንጀል ሲፈጽም እጅ ከፍንጅ ካልተያዘ በስተቀር ያለጉባኤው ፈቃድ በማንኛውም አካል አይታሰርም / አትታሰርም በተጠቀሰው ወንጀል ሕጋዊ እርምጃ የወሰደ አካል ለጉባኤው የማሳወቅ ግዴታ አለበት :: " በሚል እንዲቀመጥ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ ያቀረቡት የውሳኔ ሀሳብ በቤቱ ከፍተኛ ድምፅ ተደገፎ አልፏል ::

ቀጥሎም በአንቀጽ 4 ላይ በተሰጠው አስተያየት ርዕሱ ለቅጣት የሚያበቁ ምክንያቶች በሚል እንዲሻሻልና ቀጥሉ በሥሩ ያለው ዐረፍተ ነገር ወጥቶ በ "ሀ" እና "ለ" የተቀመጡት ንዑሳን አንቀጾች እንዳሉ እንዲቀመጡ አቶ ተፈራ መስቀሌ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ሀሳብ አቅርበዋል ::



ርዕሱ እንደተባለው ሊስተካከል እንደሚችል አቶ አዲሱ ለገሠ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ ገልጸው ቀጥሎ ያለው ዐረፍተ ነገር ግን የተሟላ እንዲሆን በስተመጨረሻ "...በኋላ ተፈጻሚ ይሆናል" በሚል ቢታከልበትና መንደርደሪያ ቢሆን እንደሚሻል አመልክተዋል ::

አቶ ደበበ አበራ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ጉባኤው በ2/3ኛ ድምፅ ከተስማማበት ሊፈጸም ይችላል የሚል ታክሎበት ዐረፍተ ነገሩ ስሜት በሚሰጥ መልክ እንዲቀመጥ አሳስበዋል ::

በሌላ በኩል ደግሞ ርዕሱ " ለመሰረዝ የሚያበቁ ምክንያቶች" ተብሎ ይቀምጥ የሚል ሀሳብ በአቶ አብዱራዛቅ መሐመድ ከክልል 14 የቀረበ ሲሆን በአንቀጽ 5 ከተደነገጉት ቅጣቶች አንዱ ለተወሰነ ጊዜ መታገድ እና ከጉባኤው መሰናበት በመሆኑና በአንቀጽ 4 "ሀ " እና "ለ" የተቀመጡትም ከጉባኤው አባልነት ሊያስርዙ የሚችሉ ምክንያቶች በመሆናቸው ርዕሱ መቀየር እንደሚያስፈልግ "ተፈጻሚ ይሆናል" የሚለው መታከል እንዳለበት አቶ አሊ አብዶ ከክልል14 ሀሳብ አቅርበዋል ::

ይህንኑ ጉዳይ በተመለከተ አቶ ታደሰ አለማየሁ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ከጉባኤው መሰረዝ የመጨረሻው እርምጃ በመሆኑ ይህን እርምጃ የሚያስወስዱ ምክንያቶች በዝርዝር ተቀምጠው ሊገቡ እንደሚገባቸው ገልጸዋል ::

በአንቀጽ "ሀ" እና "ለ" የተቀመጡት ከጉባኤ ስለመሰረዝ በሚል ንዑስ ርዕስ ሥር ሆነው ለዲስፕሊን ኮሚቴ መነሻ የሚሆኑ ነጥቦች በአንቀጽ 24 ንዑስ አንቀጽ 2 ሥር ይቀመጥ የሚል ሀሳብም በአቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ የቀረበ ሲሆን የተቀመጡት ጥፋቶች ያጠፋ አባልም በአንቀጽ 5 መሠረት ይቀጣል በሚል ቢቀመጥ የተሻለ ይሆናል ሲሉ አቶ አህመዲን ኢብራሂም ከክልል 4 ጠቁመዋል::

ከቤቱ በቀረቡ አስተያየቶች መሠረት አንቀጹ ተስተካክሎ የውሳኔ ሃሳብ እንደሚቀርብበት ሊቀመንበሩ ገልጸው ጉባኤው ከቀኑ 7:00 ለምሳ ተነስቷል ::

ከምሳ ዕረፍት በኋላ ከቀኑ 9:10 ሰዓት የጉባኤው ዋና ፀሐፊ 521 የጉባኤ አባላት በአዳራሹ ውስጥ እንደሚገኙ ጠቁመው ምልአተ ጉባኤው መሟላቱ ጉባኤ ውይይቱን መቀጠል እንደሚችል አሳስበዋል ::

የጉባኤው ሊቀመንበር ጧት በክፍል አንድ አንቀጽ 4 ላይ በስፋት ውይይት መደረጉን ጠቁመው አመራሩ የአንቀጹን ማሻሻያ እንዳቀረበና በጉባኤው ዋና ፀሐፊ በአቶ አዲሱ ለገሠ እንደሚገለጽ አመልክተው አቶ አዲሱ ለገሠ ማሻሻያውን እንደሚከተለው አቅርበዋል ::

" አንቀጽ 4 ለትጣት የሚያደርሱ ምክንያቶች

አንድ የጉባኤው አባል

ሀ. በጉባኤው ውስጥ ሆነ ከጉባኤው ውጭ ሁከት መፍጠር ወይንም ለሁከት ማናሳሳትና ጉባኤው እንዳይካሄድ እንቅፋት ሲሆን ፣

ለ. በተከታታይ 8 ቀናት ያለበቂ ምክንያት ከስብሰባ ሲቀር ፣

ሐ. የስብሰባ ሥነ ሥርዓት በተከታታይ ጥሶ ሲገኝ ፣

መ. ሌሎች የዲስፕሊን ግድፈቶች ሲገኙ

በአንቀጽ 5 ያለው ቅጣት ሊፈጸምበት /ባት ይችላል ::"

በቀረበው ማሻሻያ አንቀጽ 4 / ሐ / "የስብሰባ ሥነ ሥርዓት በተከታታይ ጥሶ ሲገኝ " ሲል ተከታታይነቱ ለስንት ጊዜ እንደሆነ እንዲብራራ ተጠይቆ ጉባኤው በአጠቃላይ በፅንስ ሐሳቡ ላይ ከተስማማ ተከታታይነቱ ለምን ያህል ጊዜ እንደሆነ እንዳስፈላጊነቱ ሊወስን እንደሚችል የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ አስረድተዋል ::

በሌላ በኩል ከክልል 14 ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ የቀረበውን ማሻሻያ ሀሳብ በመቃወም የጉባኤው አባላት በሕዝብ የተመረጡ በመሆናቸው አልወከሉኝም ብሎ ማንሳት የሚችለው የመረጣቸው ሕዝብ እንጂ 85% አንድ ድርጅት በሚሳተፍበት ጉባኤ መሆን እንደሌለበት ፣ ጉባኤው ያስወጣ ከተባለም አንስተኛውን ወገን በድምፅ ብልጫ ስለሚያስወጣው የመረጣቸውን ሕዝብ እንደሚጎዳ ፣ ከስብሰባ መቅረት የማኩረፍ ምልክት መሆኑና ምልዓተ ጉባኤ እንዳይሞላ ስለሚያደርግ የፖለቲካ ፍላጎትን ማስፈጸሚያ መንገድ እንደሆነ ገልጸው በአንቀጽ 4 "ሀ" እና "ለ" ላይ የቀረበው ማሻሻያ እንደሚቃወሙት አስታውቀዋል ::

ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ያቀረቡትን አስተያየት በመቃወም የተለያዩ የጉባኤው አባላት ማንኛው የጉባኤው አባል ሀሳቡን የመግለጽ መብት እንዳለው ፣ ሆኖም የቀረበው የማሻሻያ ሀሳብ አጣምሞ ማቅረብ ከሥነ ሥርዓት አኳያ ተቀባይነት እንደሌለው ፣ ከጉባኤው አባላት መካከል 85% የኢሕአዴግ አባል ነው የተባለው በተጨባጭ ሲታይ ይህን ያህል አለመሆኑን ሊሰመርበት እንደሚገባ ገልጸዋል :

በመቀጠልም የቀረበው የማሻሻያ ሀሳብ በድምፅ እንዲወሰን ተጠይቆ ክፍል አንድ አንቀጽ 43 በተመለከተ ከጉባኤው አመራር የቀረበው ማሻሻያ በመደገፍ 499



2 በመቃወም ፣ 1 ድምፀ ተአቅቦ በመመዝገቡ አንቀጹ በቀረበው ማሻሻያ መሠረት እንዲሻሻል ተወስኗል ::

በማስከተልም ጉባኤው በክፍል 2 ስለጉባኤው እና ስለልዩ ልዩ ኮሚቴዎች ሥልጣንና ተግባር በተቀመጡት አንቀጾች ላይ ቀጥሎ የተለያዩ የጉባኤው አባላት በክፍሉ የተካተቱት አንቀጾች የጉባኤውንና ጉባኤው ያቋቋማቸውን ኮሚቴዎች ሥልጣንና ተግባር በግልጽ ያስቀመጡ መሆናቸውን ጠቁመው በእነዚህ ላይ በሰፊው በመወያየት ጊዜ ከማጥፋት በድምፅ በመወሰን እንዲታለፍ አሳስበዋል ::

በሌላ ክፍል 2 አንቀጽ 1/1/ ውስጥ ጉባኤው በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ላይ ተወያይቶ የማሻሻል ፣ የመቀበል ወይም ካስፈለገው አዲስ ሕገ መንግሥት ከመጀመሪያ ጀምሮ የማርቀቅ ሥልጣን እንዳለው በአቶ መለስ ዜናዊ የኢትዮጵያ የሽግግር መንግሥት ፕሬዚዳንትና የተወካዮች ምክር ቤት ሊቀመንበር የተገለጸው እንዲገባ ከክልል 14 በአቶ አብዱራዛቅው መሐመድና በአቶ አዳሙ ደገፋው ሀሳብ ቀርቦ ጉባኤው የረቂቅ ሕገ መንግሥቱን ዝግጅት ሂደትና የጉባኤው አባላት አመራረጥ ዲሞክራሲያዊነትን በተመለከተ አርብ ጥቅምት 18 ቀን 1987 ዓ.ም ተወያይቶ ውሳኔ ስላሳለፈበትና ቅዳሜ ጥቅምት 19 ቀን 1987 ዓ.ም ጉባኤው ረቂቅ ሕገ መንግሥቱን ከተረከበ በኋላ በመነሻ ሰነድነት ረቂቁን መቀበሉ ፣ ስለዚህም በድጋሚ ስለረቂቅ ሕገ መንግሥቱ መወሰን እንደማይገባ የጉባኤው ሊቀመንበር አስገንዝበዋል ::

በማያያዝም አቶ አብዱራዛቅ መሐመድ በክፍል 3 አንቀጽ 5 ንዑስ አንቀጽ 5 ላይ ፣

"ጉባኤው በኮሚቴዎች በየጊዜው የሚቀርቡለትን ሥራዎች በመመልከት ቀደም ሲል በጉባኤው ከተላለፈው ወሳኔ ወይም ከተደገፈው የክርክር መንፈስ ጋር የሚመሳሰሉ መሆናቸውን ወይም አለመሆናቸውን ይገመግማል የሚመሳሰሉ ሆነው ያላገኛቸው እንደሆነ ከመመሪያው ጋር እንደገና እንዲሠሩ ያደርጋል :: "

የሚለው በክፍል 2 አንቀጽ 4 ሆኖ እንዲገባ ሀሳብ አቅርበው በጉባኤው ተቀባይነት አግኝቷል ::

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር የተደረገው ማሻሻያ ታክሎበት ክፍል 2 በአጠቃላይ በድምፅ እንዲጸድቅ ሀሳብ አቅርበው በመደገፍ 491 ፣ በመቃወም 12 ፣ ድምፀ ተአቅቦ 9 ተመዝግቦ ክፍል 2 ከነማሻሻያው ጋር በቀረበበት መልኩ እንዲቀመጥ ተወስኗል ::

አስከትሎም ውይይቱ በክፍል 3 ሥር ባሉት አንቀጾች ላይ ቀጥሎ በአንድ በኩል በክፍሉ የተጠቀሱት አንቀጾች የጉባኤው ሊቀመንበር ዋና ፀሐፊ እና ምክትል ፀሐፊ

ሥልጣንና ተግባር የሚመለከቱና በግልጽ የተቀመጡ መሆናቸውን ፣እንዲሁም ጉባኤው የመረጣቸው የአመራር አባላት ውስጠ ደንብ ከመቅረቡ በፊት ጀምረው ሲያከናውኗቸው የነበሩ ተግባሮቻቸው እንደሆኑ በተግባር በግልጽ የታዩ በመሆናቸው በክፍል 3 የተቀመጡት አንቀጾች እንዳሉ በድምፅ እንዲታለፉ ሲገልጽ በሌላ በኩል ተጨባጭ የሥልጣን ጉዳዮች በመሆናቸው ጉባኤው በአንቀጾቹ ላይ እንዲወያይበት ሀሳብ ቀርቧል ::

በመቀጠልም ከክልል 14 ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከአገር ውስጥም ሆነ ከውጭ ፓርላማዎች አሠራር ሰብሳቢው በማንኛውም ዓይነት ውይይት ለአንዱ ወገን ወግኖ እንደማይከራከር ጠቁመው የግራና የቀኙ ሀሳብ ለቤቱ አቅርቦ ውይይት እንዲደረግበት ማድረግ መሆኑ ገልጸዋል ::

አስከትለውም የጉባኤው ሊቀመንበር ይህ ጉባኤ እንጂ ፓርላማ አለመሆኑን በተደጋጋሚ መገለጹን ፣ ጉባኤው ለፓላማ አሠራር ብቻ ሳይሆን ከማንኛውም የስብሰባ ሥነ ሥርዓት የሚማረው ነገር ሊኖር እንደሚችል አብራርተዋል ::

በሌላም በኩል ከክልል 14 አቶ ታሪኩ ፅጌ ጉባኤው በሥነ ሥርዓትና አግባብ ባለው መንገድ እንዲመራ አመራር መርጦ የውስጠ ደንብ በማውጣት ላይ እንደሚገኝ ጠቁመው የአመራር አባላት እንደጉባኤ አባልነታቸው ቢያጠፉ የሚቀጡበት አንቀጽ ሲኖር ፣ እንደአመራር አባልነታቸው ሲያጠፉ የሚዳኙበት ወይም ጉባኤው ሊቆጣጠራቸው የሚችልበት አንቀጽ እንዲጨመር ጠይቀዋል ::

የጉባኤው ዋና ፀሐፊ ለዚህ በሰጡት ምላሽ የጉባኤው አመራር አባላት እንደማንኛውም የጉባኤ አባል ጥፋት ካጠፉ በደንቡ መሠረት እንደሚቀጡ የጉባኤው አመራር አባላት ራሳቸውን የሾሙ ሳይሆኑ በጉባኤው ስለተመረጡ ከማንኛውም የጉባኤ አባል ራሳቸውን የበላይ እንደማያደርጉ ፣ የአመራር አባላት በአመራር ተግባራቸው ጥፋት ቢያጠፉ የተለየ የቅጣት አንቀጽ ይኑር ከተባለ ሀሳቡን ያቀረቡት አባል የመነሻ ሀሳብ ማቅረብ እንደሚችሉ ቢጠቆሙ የመነሻ ሀሳብ አላቀረቡም ::

ቀጥሎም አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 አቶ ግርማ ብሩ ከክልል 4 ለአመራሩ የተለየ የመቆጣጠሪያ ደንብ ያስፈልጋል የተባለውን ሀሳብ በመቃወም እስከ አሁን በታየው ልምድ ለአመራር አባላት ተብሎ የተለየ ሕግ እንደማይወጣ ፣ ይውጣ እንኳን ቢባል ከተለመደው አሠራር ውጭ ከመሆኑም በላይ ለአፈጻጸም አስቸጋሪ እንደሚሆን ፣ ጉባኤው በአመራር አባላቱ በኩል ችግር አለ ብሎ ካመነ ራሱ የመረጣቸው ስለሆኑ የመሻር መብት እንዳለው ገልጸው እንደማንኛውም አባል ደግሞ በውስጠ ደንቡ መሠረት መቅጣት እንደሚቻል አስረድተዋል ::

በዚሁ ውስጠ ደንብ ክፍል 3 ውይይቱ ቀጥሎ የጉባኤው አመራር ሁለት ፀሐፊዎች ከሚኖረው አንድ ፀሐፊ ፣ አንድ ሊቀመንበርና ምክትል ሊቀመንበር





እንዲኖሩት ቢደረግ የሚል ሀሳብ ቀርቦ ሀሳቡ የአመራር አባላቱ ከመመረጣቸው በፊት መቅረብ የነበረበት እንደሆነ ተገጿል ::

በሌላም በኩል የዲስፕሊን እርምጃዎች መወሰዳቸውን የሚቆጣጠረው ማን እንደሆነ እንዲብራራ ከክልል 5 በአቶ መሀሙድ ድሪር ተጠይቆ ፣ ከምክትል ፀሐፊው ሥልጣንና ተግባር አንዱ የአስተዳደር ነክ ጉዳዮችን ይመራል እንደሚልና የዲስፕሊን ኮሚቴው በአስተዳደር ሥር ስለሆነ ምክትል ፀሐፊው እንደሚቆጣጠር በጉባኤው ዋና ፀሐፊ በአቶ አዲሱ ለገሠ ምላሽ ተሰጥቷል ::

በማስከተልም ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል አቶ ተስፋዬ ፋቻላ የጉባኤው ተሳታፊዎች የሕክምና ፣ የምግብና የመኝታ አገልግሎት ማን እንደሚቆጣጠረው በውጠ ደንቡ ውስጥ በግልጽ ስላልተመጠ በማን ሥር እንደሆነ ጠይቀው በውስጠ ደንቡ ማስፈሩ አስፈላጊ ስላልሆነ እንጂ በአስተዳደር ኮሚቴ ሥር እንደሆነ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ አስታውቀዋል ::

በውስጠ ደንቡ ክፍል 3 በስሀተት አንቀጽ 5 የተባለው አንቀጽ 4 ተብሎ እንዲስተካከል " የመሠረታዊ ኮሚቴዎች ተግባርና ኃላፊነት " የሚለው አንቀጽ 5 " የመሠረታዊ ኮሚቴዎች ሰብሳቢዎች ተግባርና ኃላፊነት " የሚለው አንቀጽ 6 እንዲሆን የጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ አሳስበዋል ::

በመቀጠልም ከክልል 14 አቶ አብዱራዛቅ መሐመድ ጉባኤው የሥራውን ሂደት ለማቀላጠፍ 10 ኮሚቴዎች ማቋቋሙን አውስተው ኮሚቴዎቹ በውይይታቸው ወቅት የሀሳብ ልዩነቶች ካጋጠሟቸው የአናሳና የአብላጫ ሀሳቦችን በሪፖርቶቻቸው አካትተው ለጉባኤው እንዲያቀርቡ የሚል አንድ አንቀጽ ቢታከል ጉባኤው ልዩነቶቻቸውን አይቶ ጠቃሚውን ሀሳብ ለመውሰድ እንደሚችል ሀሳብ አቅርበዋል ::

ከላይ ለቀረበው ሀሳብ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ በሰጡት ምላሽ እያንዳንዱ ኮሚቴ በተለያዩ ጉዳዮች ተወያይቶ ሀሳቡን ለጉባኤው ሲያቀርብ እንደኮሚቴው ሀሳብ የአብላጫው ድምፅ ፣ የአናሳውን ሀሳብ ደግሞ በልዩነት በአናሳው የኮሚቴው አባላት እንደሚቀርብ በመጠቆም መቅረብ እንዳለበት አስገንዝበው ቤቱ በዚህ ፅንሰ ሐሳብ በመስማማቱ ክፍል 3" የመሠረታዊ ኮሚቴዎች ሥልጣንና ተግባር " በሚለው ሥር" ኮሚቴው በኮሚቴነቱ ካለው ሀሳብ በተጨማሪ ልነቶችን ለጉባኤው ያቀርባል " የሚል ማሻሻያ ተጨምሮና በአጠቃላይ በክፍል 3 የተደረጉ ማሻሻያዎች ታክለው ድምፅ እንዲሰጥበት ተጠይቆ 513 ድጋፍ ፣ 1 ተቃውሞ ፣ 1 ድምፀ ተአቅቦ በመመዝገቡ ክፍል 3 ከነማሻሻያው ተቀባይነት አግኝቶ ጉባኤው ለሻይ ዕረፍት ተነስቷል ::

ከሻይ ዕረፍት በኋላም ጉባኤው ውይይቱን በክፍል 4 ላይ የቀጠለ ሲሆን በክፍል 4 አንቀጽ 1 እና 2 የስብሰባ ቀናትንና የሥራ ሰዓትን የሚመለከት ሲሆን

በአንድ በኩል  አንቀጾቹ እንዳሉ እንቀበላቸው የሚል ሀሳብ ሲቀርብ በሌላ በኩል የእስልምና ሃይማኖት ተከታዮች አርብ ከቀኑ 5:00 ሰዓት ጀምሮ የሃይማኖታቸውን ሥርዓት ማከናወንና መከታተል ስለሚፈልጉ የሰዓት መሻሻል እንዲደረግ ሀሳብ ቀርቧል ::

ሊቀመንበሩ በበኩላቸው የእስልምና ሃይማኖት ተከታዮች መብት መጠበቅ ስላለበት አርብ በመደበኛው የመንግሥት የሥራ ሰዓት ጉባኤው የሚቀጥሉ ውይይቱን ካበቃ ችግሩ እንደሚቃለል አስገንዝበዋል ::

በሌላ በኩል የጉባኤው የሥራ ሰዓት ከሰኞ እስከ ቅዳሜ 3:00--6:00 ፣ ከሰዓት በኋላ ከ8:00--11:00 ሰዓት እንዲሆን ሀሳብ ሲቀርብ ከሰዓት በኋላም ዕረፍት እንዲሆን ተጠይቋል ::

በማስከተልም አርብ ዕረፍት ሆኖ ዕሁድ ሥራ ቢሆን ከክፍለ ሀገር የመጣን ሰዎች አንዳንድ ዕቃዎች እንድንገዛ ቢደረግ የሚል ሀሳብ ተሰንዝሯል ::

አስተያየቶቹን በተመለከተ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ በሰጡት ምላሽ ቅዳሜ ከሰዓት በኋላ ጉባኤው እንዲያርፍ የአመራር አካሉ ቢያሳስብም ተግባሩን ለማፋጠንና ጊዜን ለመሻማት ቅዳሜ ሙሉ ቀን መወያየት እንዳለበት ማመኑን ፣ ጉባኤው በውስጠ ደንቡና በሌሎች ጉዳዮች አንድ ሳምንት ማጥፋቱን ፣ ከዚህ አኳያ የአርብ ጧቱን ሰዓት ማሻሻል ብቻ በቂ እንደሆነ አመልክተዋል ::

ከዚህም በማያያዝ የጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ የሕገ መንግሥት ጉባኤ አባላት በሕገ መንግሥቱ ላይ ተወያይተው ለማፅደቅ ስለመጡ ሌላ ሥራ እንደሌላቸው ከስብሰባው ሰዓት ውጭ ባለው ጊዜ ዕቃ ለመግዛት እንደሚችሉ ገልጸው በአዲስ አበባ ያሉ የመንግሥት ሠራተኞች ማታ በዕረፍት ጊዜ ሥራቸውን ማከናወን እንደሚችሉ አስገንዝበዋል ::

ክፍል 4 አንቀጽ 2 የሥራ ሰዓት በሚለው ሥር የአርብ ቀን የጉባኤው የሥራ ሰዓት ጧት 3:00 እስከ 5:30 ፣ ከሰዓት በኋላ ደግሞ ከ9:00 እስከ 12:00 ሰዓት ሆኖ ተሻሽሎ አንቀጽ 4 ንዑስ አንቀጽ 1 እና 2 ለድምፅ ቀርቦ በአብላጫው የጉባኤው አባላት ተደግፎ አልፏል ::

በመቀጠልም አንቀጽ 3 የውሳኔ ሀሳብ አቀራረብ ሲል አንቀጽ 4 ደግሞ የአጀንዳ አቀራረብ ስለሚል የውሳኔ ሀሳብ የሚቀርበው አጀንዳ ከቀረበና ውይይት ከተደረገበት በኋላ ስለሆነ ቅድም ተከተላቸው እንዲስተካከል ቢደረግ ሲሉ አቶ ደስታ አጥናፉ  ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ሀሳብ አቅርበው ቤቱ ተቀብሎታል ::



በሌላ በኩል ጉባኤው የተለያዩ ኮሚቴዎች እንዳቋቋመ አቶ መሀሙድ ድሪር ከክልል 5 ጠቁመው በአንቀጽ 4 ንዑስ አንቀጽ 2/ለ/ ላይ"...ኮሚሽኖች..."የሚለውን ለምን በውስጠ ደንቡ እንደገባ እንዲብራራላቸው ጠይቀዋል ::

ለዚህም የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ ጉባኤው ኮሚሽኖች ያቋቁማል የሚል ሀሳብ እንደነበረ ጠቁመው አሁን ግን የተቋቋሙት ኮሚቴዎች ሥራውን ለመሥራት ስለሚችሉ "ኮሚሽኖች" የሚለው ቃል ሊሰረዝ እንደሚችል ገልጸዋል ::

በማስከተልም አቶ ጫላ ወርዖፋ ከክልል 4 በአንቀጽ 4 ንዑስ አንቀጽ 1 እና 2 የተቀመጡት ነጥቦች እንዲብራሩላቸው ስለጠየቁ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ በአንቀጽ 4 ንዑስ አንቀጽ 1 ላይ የተቀመጠው ሀሳብ የስብሰባ አጀንዳ ሲያዝ የጉባኤው 1/3ኛ የድጋፍ ድምፅ ማግኘት እንዳለበት ለመግለጽ እንደሆነ ፣ ንዑስ አንቀጽ 2 ግን የጉባኤው አጀንዳዎች ቅደም ተከተል የሚዘጋጅባቸው ጉዳዮች የሚያሳይ መሆኑን አብራርተዋል ::

በመቀጠልም አቶ ካሚል አህመድ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል አንቀጽ 5 "ጉባኤው በሌላ አኳሃን ካልተወሰነ በስተቀር የጉባኤው ስብሰባ ለሕዝብ ግልጽ እንዲሆን አፈጻጸሙ በዝርዝር መመሪያ ይወሰናል " የሚለው ምን ለማለት እንደሆነ እንዲብራራላቸው ጠይቀዋል ::

ለዚህም የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ በሰጡት ምላሽ "ካልተወሰነ" የሚለው "ካልወሰነ" በሚል እንዲስተካከል ካሳሰቡ በኋላ ጉባኤው ወይይቱ በሚጥር ይሁን ብሎ ካልወሰነ ጋዜጠኞች ፣ እንግዶችና ታዛቢዎች ሊገኙ እንደሚችሉና የጉባኤው ወይይትም በመገናኛ ብዙሃን እንደሚተላለፍ ለመግለጽ ተፈልጎ እንደሆነ ፣ "አፈጻጸሙ በዝርዝር መመሪያ ይወሰናል" የሚለውም ጉባኤው ለማንም ይፋ በመሆኑ አዳራሹ ከሚይዘው በላይ በሰው እንዳይጨናነቅ የአመራር አካሉ ከጉባኤው ውክልና አግኝቶ የማስተናገጃ ሥነ ሥርዓት ለማውጣት እንዲችል ታስቦ የተቀመጠ አንቀጽ መሆኑን አስረድተዋል ::

ከአንቀጽ 5 እስከ አንቀጽ 7 ያሉት ግልጽ መሆናቸውን የተለያዩ የጉባኤው አባላት ጠቁመው ጉባኤው በድምፅ እንዲወስንና እንዲያሳልፋቸው በቀረበው ሀሳብ መሠረት ባሉበት መልክ እንዲያልፉ በሙል ድምፅ ተቀብሏቸዋል ::

አቶ አዳሙ ደገፋው ከክልል 14 አንቀጽ 8 ንዑስ አንቀጽ 2 " ሊቀመንበሩ እንደአስፈላጊነቱ መዝገቦ በያዘው የተናጋሪዎች ቅደም ተከተል መሠረት እንደአስፈላጊነቱ መዝገቦ በያዘው የተናጋሪዎች ቅደም ተከተል መሠረት ሀሳባቸውን እንዲገልጹ ይፈቅድላቸዋል " የሚለው ምን ያህል ተግባራዊ እንደሚሆን ጠይቀው

ንዑስ አንቀጹ" የተናጋሪዎችን ቅደም ተከተል በመመዝገብ በተራ ያወያያል" ተብሎ እንዲሻሻል ሀሳብ አቅርበዋል ።

ለዚህም የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ ሊቀመንበሩ እንደአስገላጊነቱ በቅደም ተከተል ሊሚዘገብ እንደሚችል ፣ ሁሉጊዜ ይመዘገባል ማለት አስቸጋሪ እንደሚሆን ፣ ሆኖም አወያይ ነጥቦች ከሆኑ በቅደም ተከተል መዝግቦ ማወያየት እንደሚችል አስገንዝበዋል ።

ቀጥሎም ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 በአንቀጽ 8 ላይ 3 ገጽ ጽፈው እንደመጡ ፣ በዚህ ጉባኤ ላይ በርካታ ተሳታፊ ስላለ በያንዳንዱ ጉዳይ ላይ ደጋፊንና ተቃዋሚን መዝግቦ ማወያየት ቢከብድም ጉዳዩ አከራካሪ ከሆነ ደጋፊና ተቃዋሚ በቅድሚያ ተመዝግበው እኩል በእኩል ማወያየት አስፈላጊ እንደሆነ አሳስበው በርካታ ሰዎች ሀሳባቸውን ለመግለጽ እጃቸውን አውጥተው ዕድል ሳያገኙ እንደሚቀሩ ገልጸዋል ።

ለዚህም የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ ማሳሳቢያው መድረኩ ዲሞክራሲያዊ እንዳልሆነ የሚጠቁም ስለሆነ ትክክል አለመሆኑንና ተቀባይነት እንደሌለው ገልጸው ማንኛውም የጉባኤው አባል ሀሳቡን የመግለጽ መብቱ የተጠበቀ መሆኑን ፣ እስከአሁን አመራሩ ከሁሉም አቅጣጫ እያየ ሲያወያይ እንደቆየና ከተናጋሪዎች ብዛት አኳያ ጥቂት ሰዎች እጃቸው አውጥተው ከቤቱ ወደ ውሳኔ እንዲሄድ በመጠየቁ ሳይናገሩ እንደቀሩ አመልክተዋል ።

በማያያዝም አቶ ግርማ ብሩ ከክልል 4 በ1955 ዓ.ም በኢትዮጵያ ፓርላማ ደጋፊና ተቃዋሚ በሚል ከተመዘገቡ በኋላ ውይይት ይካሄድ እንደነበር ጠቁመው ይህ ግን ቋሚ የፓርላማ ደንብ እንዳልሆነ አብራርተዋል ።

በመጨረሻም አንቀጽ 8 እንዳለ እንዲቀመጥ ተቀባይነት አግኝቶ ጉባኤው የዕለቱን ውይይቱን ከምሽቱ 12:05 ሰዓት ተጠናቋል ።





ጥቅምት 25 ቀን 1987 ዓ.ም በሕገ መንግሥት አጻራሽ ስብሰባ ከጧቱ በ3:00 የተጀመረው የሕገ መንግሥት ጉባኤ ስብሰባ 523 የጉባኤ አባላት የተገኙ ሲሆን ጉባኤው የመሩት የጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ በቅድሚያ የዕለቱን አጀንዳዎች ፣

1. በሕገ መንግሥት ጉባኤ ውስጠ ደንብ የተጀመረውን ውይይት ማጠናቀቅ ፣
2. ቀደም ሲል ለጉባኤተኞች የተበተነውን ቁጥር 3 ቃለጉባኤን ማፅደቅ እና
3. አስተዳደራዊ ጉዳዮችን በተመለከተ መወያየት ፣

የሚሉ እንደሆነ ገልጸው በውስጠ ደንቡ ረቂቅ ክፍል 4 አንቀጽ 9 ላይ አስተያየት ካለ ሊቀርብ እንደሚችል ጋብዘዋል ።

በዚህም መሠረት አንድ የጉባኤው አባል ምክር ስለመጠየቅ የሚለው አንቀጽ 9 በጉባኤው ሥልጣንና ተግባር ሥር ሊካተት የሚችል በመሆኑ ወደ ክፍል 2 እንዲዛወር አሳስበዋል ።

ለዚህም የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ በጉባኤው ሥልጣንና ተግባር የተካተተው ለጉባኤው ስኬት ማንኛው ሰው ጠርቶ የማነጋገርና ሰነድ የመመርመሩ ጉዳይ በውይይት ጊዜ ለቤቱ ግንዛቤ እንዲረዱ የውይይቱን አካሄድ የተሻለ ፊር ሊያስይዙ የሚችሉ የባለሙያዎችና የሌሎች ሰዎች ምክር ከመጠየቁ ሁኔታ በባህርይው የተለየ መሆኑን መገንዘብ እንደሚገባ ገልጸዋል ።

በሌላ በኩል ደግሞ አቶ አባይ ፀሐዬ ከክልል 1 በሰነዘሩት አስተያየት አንቀጽ 9 በክፍል 2 ሥር መጠቃለሉን ተቀብለው በሁለቱም አንቀጾች ያልተጠቀሰው የሕዝብን አስተያየት ተቀብሎ ማስተናገጃ መንገድ ግን በውጠ ደንቡ መካተት እንደሚገባው አመልክተዋል ።

ለዚህም የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ የሕዝብ አስተያየት የሚስተናገድበት መንገድ በጽሑፍ ሆኖ ለጉባኤው ዋና ፀሐፊ ወይም ከተቋቋሙት ኮሚቴዎች መካከል ለሚመለከተው ወይም በጽሑፍ የመጣውን አስተያየት ኮሚቴው ተመልክቶ ከመዘነው በኋላ አስተያየት አቅራቢው ቀርቦ በማስረዳት ሊሆን እንደሚችል ገልጸዋል ።

የጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ አስተያየትን በጽሑፍ የማቅረብ ዕድል ቀድሞውንም ቢሆን በክፍል 2 የተቀመጠ እንደሆነ ገልፀው ያልተጠቀሰው ግን በአካል ቀርቦ ማስረዳት እንደሆነ አስገንዝበዋል ።

አቶ አባይ ፀሐዬ ከክልል 1 አስተያየት የማቅረቡ ሀሳብ በፍፁም አልተጠቀሰም አለማለታቸውን ጠቁመው በውስጠ ታዋቂ የተቀመጠ ስለሆነ በግልጽ እንዲታይ ተደርጎ እንዲቀመጥ አሳስበዋል ::

የጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ በበኩላቸው ቤቱ ከተቀበለው የሕዝብ አስተያየት መቀበልን በተመለከተ የቀረበውን ሀሳብ ራሱን ችሎ በአንድ አንቀጽ ማስቀመጥ የሚለውንና አንቀጽ 9ን ደግሞ ወደ ክፍል 2 አንቀጽ 1 ማዛወር የተባለውን ማድረግ እንደሚቻል ገልጸዋል ::

ቀጥሎም አንቀጽ 9 የመንግሥት ባለሥልጣናትንም ሆነ ሌሎች ግለሰቦችን ለምክር መጥራት የሚመለከት ተፈላጊ አንቀጽ ስለሆነ እንዳለ ቢቀመጥ ይሻላል የሚል አስተያየት ቀርቧል ::

ዶ/ር ተከተል ፎርሲዶ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ደግሞ አንቀጽ 9 ወደ ክፍል 2 ከማዛወር ይልቅ ፣

አንቀጽ 9 . ምክር ስለመጠየቅና አስተያየት ስለመቀበል ፣

ሀ. ጉባኤው አስፈላጊ ሆኖ ሲያገኘው የመንግሥት ባለሥልጣንንም ሆነ ሌሎች ግለሰቦችን ለምክር መጥራት ይችላል ::

ለ. ከተለያዩ ግለሰቦችም ሆነ አካባቢዎች የሚመጡት አስተያየቶች መቀበል ይችላል ::

ተብሎ ተሻሽሾ ቢቀመጥ በአቶ አባይ ፀሐዬ የቀረበውን ሀሳብም ሊያካትት እንደሚችል የሚል ሀሳብ አቅርበዋል ::

አቶ እጅጉ ገ/ሚካኤል ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል በበኩላቸው የዶ/ር ተከተል ፎርሲዶ ማሻሻያ እንደሚደግፉት ገልጸው በ «ለ» ሥር ያለውን ግን ከውጭ የሚቀርቡ አስተያየቶችንም ሆነ ሀሳቦች መርምሮ ማየት ይቻላል ተብሎ እንዲቀመጥ ሀሳብ አቅርበዋል ::

በሌላ በኩል አቶ ካሚል አህመድ ከደቡብ ኢትዮጵያ ክልል በሰነዘሩት አስተያየት ምክር መጠየቅ የሚለው ጉባኤው በሚወያይባቸው ጉዳዮች ላይ ጉባኤተኛው ማብራሪያ ከፈለገ የሆነ አካል ጠርቶ ምክር እንዲሰጥ ማድረጉ ሲሆን የሕዝብ አስተያየት መቀበል ደግሞ ከዚህ የተለየ ስለሆነ ሁለቱን አደባልቆ በአንድ አንቀጽ ሥር ማስቀመጥ እንደማይገባ ጠቅሰዋል ::



ከዚያም አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 በሰጡት አስተያየት በክፍል 2 አንቀጽ 3/መ/ ላይ ፀሐፊው ወደ ጉባኤው የሚላኩትን ወይም በእጅ የሚሰጡትን ጽሑፎችና ደብዳቤዎች ተቀብለው እንደሚመሩ የተቀመጠ ስለሆነ አንቀጽ 9 ያለምንም ተጨማሪ እንዳለ መታለፍ እንዳለበት አሳስበዋል ::

ቀጥሎም የጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ አንቀጽ 9 በተመለከተ 3 አስተያየቶች መስጠታቸውን ፣ እነሱም 1ኛ አንቀጽ 9 ያለ ቦታ የገባ ስለሆነ ወደ ክፍል 2 ይዛወር 2ኛ በአንቀጹ ላይ አስተያየት የመቀበል መንገድ ተጨምሮበት በሁለት ንዑስ አንቀጾች ተከፍሎ ይቀመጥ ፣ 3ኛ አስተያየት መቀበል ምክር ከመ ጠየቅ የተለየ ስለሆነ ለብቻው ሌላ አንቀጽ ይከፈትለት የሚሉ እንደሆኑ ገልጸው የተነሱትን ነጥቦች ደረጃ በደረጃ ለማየት እንዲቻል ቅድሚያ ስለቅርፁ ማለትም ስለአንቀጽ 9 መዛወር አስተያየት እንዲሰጥበት አሳስበዋል ::

በሌላ በኩል አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 በሰጡት አስተያየት ቅርጹ የመጨረሻው ረቂቅ ሲዘጋጅ ቢስተካከል እንደሚሻል ገልጸው አስተያየትን የመቀበል ጉዳይ አንዳንድ የአሠራር መንገድና የሕዝብ መብት ራሱን በቻለ አንቀጽ እንዲካተት ሀሳብ አቅርበዋል ::

ከዚያም ሊመንበሩ ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ አስተያየት መቀበል ራሱን በቻለ አንቀጽ ይቀመጥ ከሚለው የተለየ አስተያየት ካለ እንዲቀርብ ቤቱን ጠይቀዋል ::

ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 በበኩላቸው ዶ/ር አብዱልመጂድ ባቀረቡት ላይ በመሠረተ ሀሳቡ እንደሚስማሙ ገልጸው የሚለዩበት ግን በጽሑፍ ለማቅረብ እንዲፈቀድላቸው ጠይቀው ተፈቅዶላቸዋል ::

ቀጥሎም አቶ ማሞ ጎዴቦ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል በበኩላቸው ምክር መጠየቅ አንዳንድ ሕግን ፣ ሰብአዊ መብትን ወዘተ...በተመለከተ ለጉባኤው ማብራሪያ ሲያስፈልግ ዕውቀትና ብቃት ያላቸውን ሰዎች መጥራቱ የሚመለከተው በአብዛኛው ቴክኒካዊ በመሆኑ ለብቻው እንዲቀመጥ ፣ አስተያየት መቀበል የሚለው ደግሞ ሌላ አንቀጽ እንዲከፈትለት የሚለውን እንደሚደግፉ ገልጸዋል ::

ከዚያም አቶ መኩሪያ ታፈሰ ከክልል 14 የጉባኤው ተግባር የኢትዮጵያን ሕገ መንግሥት ማፅደቅ ስለሆነና ለዚህ ደግሞ በተቻለ መጠን ከሕዝብ የሚመጣውን

ሀሳብ ተቀብሎ ማስተናገድ ሊታለፍ የማይገባው በመሆኑ አስተያየቱን የሚቀበል አንድ ኮሚቴ ተቋቋሞ ወይም ከተቋቋሙት ኮሚቴዎች መካከል አንዱ ኃላፊነቱን ተረክቦ በተቀባለው አስተያየት መሠረት የተለየ ሪፖርት አጠናቅሮ ከረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ጋር አብሮ እንዲያቀርብ ቢደረግ የሕዝብ መብት በተሻለ መልክ እንደሚጠበቅ አመልክተዋል ::

ሆኖም ጉባኤው ቀደም ሲል 10 ኮሚቴዎችን በማቋቋም የተቋቋሙት ኮሚቴዎች ከጉባኤው የሚመሩላቸውን አጀንዳዎች ብቻ ሳይሆን ከጉባኤውም ውጭ የሚመጣ አስተያየት እየተቀበሉ በመመርመር አስፈላጊ ሆኖ ሲያገኙትን ባለሙያ ጠርተው በማነጋገር በጉዳዩ ላይ ተወያይተው ለበሌቱ እንዲያቀርቡ የወሰነበት ስለሆነ የቀረበው ጥያቄ ቀደም ብሎ መመለሱን የጉባኤው ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ አስረድተው አንቀጽ 9 ዶ/ር ተከተል ፎርሶዶ ባቀረቡት ማሻሻያ መልክ ቢቀመጥ እንደሚሻል አሳስበዋል :: ከዚያም የኸው ሀሳብ ለድምፅ ቀርቦ 514 ድጋፍ ፣ 3 ድምፀ ተአቅቦ ተመዝግቦ ያለምንም ተቃውሞ ፀድቋል ::

ቀጥሎም አቶ መኩሪያ ታፈስ ከክልል 14 ድምፅ ያልሰጡበት ምክንያት ለመግለጽ ጠይቀው ስለተፈቀደላቸው ጉባኤው ከውጭ የሚመጣን ተቃውሞ ማስተናገድ እንዳለበት ያቀረቡት ሀሳብ ስላልተያዘላቸው ድምፅ ከመስጠት እንደታቀቡ ገልጸዋል ::

ከዚያም ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ከክልል 5 አንቀጽ 10 ፣ 11 ፣ 12 እና 13 ፍሬ ነገር ከዚህ ቀደም በብዙ መንገድ የተነካካና በጉባኤውም በሥራ ላይ የዋለ ስለሆነ ተቃውሞ ከሌለ አንቀጾቹ ታልፈው ወይይቱ በአንቀጽ 14 ላይ እንዲቀጥል የውሳኔ ሀሳብ አቅርበዋል :

ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 በበኩላቸው ዶ/ር አብዱልመጂድ ባቀረቡት ላይ በመሠረተ ሀሳቡ እንደሚስማሙ ገልጸው የሚለዩበት ግን በጽሑፍ ለማቅረብ እንዲፈቀድላቸው ጠይቀው ተፈቅዶላቸዋል ::

ከዚያም አቶ ተመስገን ማሞ ከክልል 14 ደግሞ በአንቀጽ 10 ሊተላለፍ የተፈለገው መልዕክት የበለጠ ግልጽነት እንዲኖረው ንዑስ አንቀጽ 2 ሊቀመንበሩ አስፈላጊ ሆኖ ሲያገኘው ሀሳቡ በጽሑፍ እንዲቀርብ ያደርጋል ተብሎ እንዲስተካከልና ንዑስ አንቀጽ 3 ደግሞ አባሉ ማሻሻያውን ከተቀበለው የሚለው ስሜት ስለማይሰጥ እንዲስተካከል ሀሳብ አቅርበዋል ::



የጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ የቀረበው የስዋስው ማስተካከያ የመጨረሻው ረቂቅ ሲጻፍ የሚደረግ እንደሚሆን ገልጸው በአንቀጽ 10 ላይ ሌላ አስተያየት ካለ እንዲቀርብ በጠየቁት መሠረት አቶ ታረኩ ፅጌ ከክልል 14 የማሻሻያ ሀሳብ ማቅረብ የማንኛውም አባል በቅድም ተከተል የሚያገኘው መብት ስለሆነ እንዳለ እንዲያልፍ ያቀረቡት ሀሳብ ተቀባይነት አግኝቶ ፀድቋል ::

ቀጥሎም የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ በአንቀጽ 11" ነገር ግን የቀረበውን ሀሳብ እቀጥልበትአለሁ የሚል ካለ ውይይቱ ሊቀጥል ይችላል:: ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 በበኩላቸው ዶ/ር አብዱልመጂድ ባቀረቡት ላይ በመሠረተ ሀሳቡ እንደሚስማሙ ገልጸው የሚለዩበት ግን በጽሑፍ ለማቅረብ እንዲፈቀድላቸው ጠይቀው ተፈቅዶላቸዋል :: የሚል ዐረፍተ ነገር እንዲታከልበት አሳስበዋል ::

ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ከክልል 5 በበኩላቸው ከአንቀጽ 11 እስከ 13 ያሉት አንቀጾች እንዳሉ እንዲታለፉ ቢያሳስቡም በአንቀጽ 11 ላይ እንዲተከል የቀረበው ማሻሻያ አንድ አባል ለውይይት ያቀረበውን ሀሳብ ሊቀጥልበት እንደሚችል የተገለጸው ሀሳቡ ያነሳው ሰው እንደገና ሊቀጥል ካለመቻሉ አንፃር ትክክል እንዳልሆነ አቶ አለማየሁ ወርዶፋ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል አሳስበዋል ::

ሆኖም የተጠመረው ዐረፍት ነገር የሚገልጸው ሀሳቡን ያነሳ ሰው ሃሳቡን እንደገና እንደሚቀጥል ሳይሆን ከሀሳብ አቅራቢው ሌላ ሰው እንደሆነ የጉባኤው ምክትል ፀሐፊ አቶ አባተ ኪሾ ገልጸዋል ::

ከዚያም አቶ አዳሙ ደገፉ ከክልል 14 በአንቀጽ 14 ንዑስ አንቀጽ 13 የተቀመጠው አንድ የጉበኤ አባል አሳማኝ ምክንያት በማቅረብ ውይይቱ እንዲቀጥል የማስደረግ መብቱ ሊቀመንበሩ እንዲገድብበት የሚያደርግ በመሆኑ " ተቃዋሚው ወገን አሳማኝ ምክንያት ካለው ጉበኤውን ጠይቆ ክርክሩን እንዲቀጥል ለማድረግ ይችላል :: " የሚል ዐረፍተ ነገር እንዲታከልበት ሀሳብ አቅርበዋል ::

ሆኖም ሊቀመንበሩም ቢሆን በቤቱ በተለያዩ መንገዶች ሊታገድ ስለሚችል የተቃዋሚውን ወገን መብት ይገድባል የሚለው ሥጋት መኖር እንደሌለበት ገልጸዋል ::

ከዚያም አቶ ሸምሰዲን አህመድ ከክልል 5 አንቀጽ 13 የሚገልጸው በአንድ ጉዳይ ላይ ውይይት ሲካሄድ ቆይቶ ጉዳዩ በሚገባ ተብላልቷልና ወደ ውሳኔ እንሂድ ብሎ ሀሳብ ማቅረብን ከሆነ የጎደላው ስላለ" በቀረበው ውሳኔ ሀሳብ ላይ 1 የድጋፍ፣ 1 የተቃውሞ ሀሳብ እንዲቀርብ ይጠይቃል ::" በቀረበው የውሳኔ ሀሳብ ላይ ድምፅ ይሰጥበታል "የሚል በንዑስ አንቀጽ 2 ላይ እንዲታከል አሳስበዋል ::

ሊቀመንበሩ ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ይህን ማከል ከፓርላማ አሠራር አንፃር ምን ያህል ጠቀሜታ እንደሚኖረው ተጠይቀው ሲያስረዱም አንድ ውይይት የሚካሄድበት ሀሳብ ተጠቃልሎ ወደ ድምፅ ከመሄዱ በፊት በተጠቃለለው ሀሳብ ላይ 1 የድጋፍና 1 የተቃውሞ ሀሳብ ቀርቦበት ለድምፅ እንዲዘጋጅ ተገቢና የተለመደ አሠራር መሆኑን ገልጸዋል ::

በሌላ በኩል ደግሞ ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ ከክልል 1 አንቀጽ 13 የያዘው ዕንስ ሐሳብ በአንድ ጉዳይ ላይ በሚገባ ውይይት ተካሂዶና ውይይቱ ይቁም በማለት ለቤቱ አቅርቦ የሚያስወስንበት መንገድ እንደሆነና ተቃውሞና ድግፍም የሚሰጥበት እንደሆነ ገልጸው በአቶ ሸምሰዲን አህመድ የታከለው ግን የውሳኔ ሀሳብ አቀራረብንና ድጋፍ አሰጣጥን የሚመለከት ፣ 1 ድጋፍ ፣ 1 ተቃውሞ ሀሳብ ቀርቦበት ለድምፅ የሚያዘጋጅ እንደሆነና ከስብሰባ አፈጻጸም የተለየ እንደሆነ አመልክተዋል ::

አቶ ሸምሰዲን አህመድ አንቀጹ የሚመለከተው ውይይቱ በስሏልና ወይይቱን እናቁም ከሆነ የውሳኔ አቀራረብ ባይጨመርበትም እንደሚስማሙ ገልጸዋል ::

በሌላ በኩል ደግሞ አቶ አባይ ፀሐዬ ከክልል 1 በአቶ ሸምሰዲን አህመድ የቀረበው ሀሳብ ውይይቱን እናቁም ወይም አናቁም በሚለው ላይ 1 የድጋፍ ፣ 1 የተቃውሞ ሀሳብ እንዲቀርብ የሚል ሳይሆን ወደ ውሳኔ ከመግባቱ በፊት በረቂቅ የውሳኔ ሀሳቡ /ሞሽን / ላይ 1 የድጋፍ ፣ 1 የተቃውሞ አስተያየት እንዲሰጥ መፍቀድ እንደሆነ ገልጸው ይህ ደግሞ ሊቀመንበሩ የድጋፍና የተቃውሞ አስተያየት እንዲሰጥ ሊጠይቅ ይችላል ካልተባለ በስተቀር በውስጠ ደንቡ ውስጥ ሳይካተት መታለፍ እንደሌለበት አሳስበዋል ::

ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ ከክልል 1 በአቶ ሸምሰዲን አህመድ የቀረበው አንቀጽ 13 ረቂቅ የውሳኔ ሀሳብ አቀራረብን አይመለከትም እንጂ ሀሳቡ ትክክል አይደለም አለማለታቸውን ጠቆመው የውሳኔ ሀሳብ አሰጣጥ በሚለው አንቀጽ 15 ላይ የሞሽን ጉዳይ ቢገባ እንደሚሻል ገልጸዋል ::

ከዚያም ሊቀመንበሩ ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ የሞሽን ጉዳይ እንደሚገባ ቢያሳስቡም አቶ ግርማ ብሩ ከክልል 4 ግን ሞሽን ማለት አንድ አባል ለውይይት የሚያቀርበው ሀሳብ በመጨረሻ በአንድ መልክ ተጠቃልሎ በሚደገፍና በሚቃወም መልኩ በሀሳብ ነጥሮ ሲወጣ ማለት እንደሆነ ገልጸው ይህንን በሚመለከትም በአንቀጽ 11 በመጠኑ የተቀመጠ ስለሆነ የሞሽን ጉዳይ ወደ አንቀጽ 15 ከሚወሰድ በአንቀጽ 11/1/ በግልጽ ቢገባ እንደሚሻል ሀሳብ አቅርበዋል ::



የጉባኤው ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ በአንቀጽ 11 የተቀመጠው ሀሳብን ስለመሳብና ሌላ ሰው ከፈለገ የተነሳውን ሀሳብ ሊቀጥልበት እንደሚችል ለማመልከት መሆኑንና ከሞሽን የተለየ እንደሆነ ገልጸው የአንቀጽ 13 መንፈስ ግን ጉባኤው በአንድ አጀንዳ ሲካሄድ የቆየው ውይይት በቂ ነውና ወደ ውሳኔ እንለፍ በሚል ከቤቱ ወይም ከአመራሩ ሀሳብ ማቅረብ መቻሉንና ይህ ተቃውሞ ከገጠመው በድምፅ የሚወሰን መሆኑን እንደሚያመለክት ፣ ውሳኔ አሰጣጡም በሞሽን ይሁን ከተባለ የውሳኔ ድምፅ በሚለው አንቀጽ 15 ላይ መግባት እንዳለበት አብራርተዋል :: አቶ ግርማ ብሩም ከክልል 4 በዚሁ ተስማምተዋል ::

በመቀጠልም የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ አንቀጽ 14 በተመለከተ በሰጡት ማብራሪያ በአንድ ጉዳይ ላይ ውይይት ሲካሄድ በቃላት፣ በዐረፍተ ነገርና በአንቀጽ ላይ ፣ እንዲሁም በጉዳዩ ዝርዝርና አጠቃላይ ነጥቦች ላይ ጥያቄና ክርክር ሊነሳ እንደሚችል ፣ ሆኖም ሁሉንም ጥያቄዎች ደባልቆ በአንድ ጊዜ ማስተናገድ ስለሚያስቸግር በቅድሚያ የቃላቱ ፣ የዐረፍተ ነገሩና የአንቀጹ ጥያቄ እልባት እንዲሰጠው ፣ ቀጥሎ ደግሞ የጉዳዩ ዝርዝር ነጥቦችና የጉዳዩ አጠቃላይ ይዘት መፍትሔ እንዲያገኝ ለማድረግ የድምፅ አሰጣጥና አወሳሰኑ አካሄድ ደረጃ በደረጃ እንዲከናወን መታሰቡን አስረድተዋል ::

ከዚያም ሊቀመንበሩ ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ በአንቀጽ 14 ላይ አስተያየት እንዲሰጥ ቢጠይቁም ባለመቅረቡ አቶ ሸምሰዲን አህመድ ከክልል 5 በአንቀጽ 15 እንዲካተት ያቀረቡት ሀሳብ እንዲገልጹ ስለተፈቀደላቸው "ውይይቱ ተጠቃልሎ ድምፅ እንዲሰጥበት ቤቱ ሲወስን የጉባኤው አመራር ወይም የጉባኤው አባል የውሳኔ ሀሳብ እንዲያቀርብ ይደረጋል :: በቀረበው የውሳኔ ሀሳብ ላይ 1 የድጋፍ ፣ 1 የተቀውሞ ሀሳብ እንዲቀርብ ይጠየቃል :: በውሳኔ ሀሳቡም ላይ ድምፅ ይሰጥበታል :: " የሚል እንዲጨመር የሚለውን አቅርበዋል ::

የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ በበኩላቸው በአቶ ሸምሰዲን አህመድ የቀረበው ሀሳብ ተጠቃልሎ የውሳኔ ድምፅ የሚከድበትን እንጂ የሞሽን ጉዳይ እንዳልሆነ ቢያሳስቡም ሀሳቡ ከተጠቃለለ በኋላ በግልጽ ድምፅ እንዲሰጥበት የመደረጉ ሁኔታ የውሳኔ ሀሳብ መሆኑን አቶ ሸምሰዲን አህመድ በድጋሚ አስረድተዋል ::

ቀጥሎም ሊቀመንበሩ ዶ/ር ነጋሶ ጋዳዳ የሞሽንም መግባት የሚቃወም ካለ እንደሚቻል በገለጹት መሠረት በቀረበው አስተያየት ውይይት ተካሂዶ ከቤቱ አባል ወይም አመራር ክርክሩ ይቁም የሚል ሀሳብ ሲቀርብ በጉዳዩ ላይ የሚካሄደው ውይይት በስኋል እናቁም ወይም አልበሰለም እንቀጥል ብሎ ቤቱ በድምፅ የሚወስነው እንጂ 1 የድግፍ 1 የተቃውሞ ሀሳብ እንዲቀርብ ማድረግ ተገቢ እንዳልሆነ ተገልጿል ።

ሊቀመንበሩ ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ የቀረበው አስተያየት ሞሽንን የሚመለከት ስላልሆነ ሌላ ተቃዋሚ ካለ እንዲናገር ዕድል ስለሰጡ አቶ ታደሰ ካሳ ከክልል 3 የተነሳው ጉዳይ በሚገባ ተብላልቷልና ውይይቱ ይቁም ተብሎ ከአመራሩ ሆነ ከቤቱ ሀሳብ እንደሚቀርብና ይህም በድምፅ የሚወሰን እንደሆነ ፣ የውሳኔ ሀሳብ /ሞሽን/ አቀራረብም ከቤቱ ሆነ ከአመራሩ የሚነሳ ሆኖ 1 ድጋፍና 1ተቃውሞ አስተያየት እንዲሰጡ ከተደረገ በኋላ የሚወሰንበት መሆኑን አመልክተዋል ።

ይሁንና የሞሽን አሠራር ከቃላት ጀምሮ ሀሳብን እያስተካከሉ መሄድን ስለሚጠይቅ ጊዜን እንደሚያጓትት ፣ በመሆኑም በተወካዮች ምክር ቤት አሠራር እንደታየው በአንድ ጉዳይ ላይ በቤቱ ውስጥ የታዩ ልዩነቶችን ሊቀመንበሩ ስሉ በማቅረብ በሁለቱ ሀሳቦች ላይ በድምፅ የሚያስወስንበት አሠራር መከተል ከሞሽን አካሄድ ተመራጭነት እንዳለው ፣ ለዚህም "ሊቀመንበሩ ልዩነቶችን ስሉ ድምፅ ይሰጣል ። "የሚል እንዲቀመጥ አሳስበዋል ።

በሌላ በኩል ደግሞ የማቆም ውሳኔ የቤቱ እንደሆነና ውይይቱን ለማስቀጠል ግን አንድ አባል ያልበሰለ ነጥብ አለ ብሎ ምክንያቱን በግልጽ ሊጠይቅ እንደሚችል ፣ ይህ ከተፈቀደለት ውይይቱ ሊቀጥል እንደሚችል ፣ ካልተፈቀደለት ግን የድምፅ አሰጣጡ እንደሚቀጥል ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 የፓርላሜንታሪ አሠራር ነው የሚል እንፎርሜሽን አቅርበዋል።

ከዚያም ለቀመንበሩ ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ የሞሽን አቀራረብ የሚደግፍ 1 ሰው ፣ የሞሽን አቀራረብን በመቃወም ደግሞ 1 ሰው አስተያየት እንዲሰጥና ጉዳዩ እንዲቋጭ አሳስበዋል ።

በዚህም መሠረት አቶ ካሪቴ ጉሉ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል የውሳኔ ሀሳብ ማቅረብ ያለበት በቤቱ ሀሳቡ አልቋጭ ያለ አከራካሪ ጉዳይ ተመርቶለት ከመረመረ በኋላ የሚያቀርብ ኮሚቴ መሆን እንዳለበት ገልጸዋል ።

አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 ደግሞ በአቶ ሸምሰዲን አህመድ የቀረበው ሀሳብ ጉባኤው ውሳኔ ላይ ከመድረሱ በፊት የውሳኔ ሀሳብ ተጨምቆ እንዲቀርብና



ክርክሩን በሚገባ የሚወክሉ 1 ደጋፊና 1 ተቃዋሚ ተናግረው ውሳኔ ይሰጥ የሚል ሲሆም ፣ በአቶ ታደሰ ካሳ የቀረበውም የሞሽን አሠራር ጊዜ ስለሚፈጅ ይቅር የሚል እንጂ ከዚህ የተለየ ስላልሆነ የክርክሩ ነጥቦች በሊቀመንበሩ አጠር ብለው ከቀረቡ በኋላ 1 ደጋፊና ሌላ ተቃዋሚ እንዲናገሩ ተደርጎ ቤቱ የመጨረሻ ውሳኔ የሚሰጥበት አሠራር ቢቀመጥ ሁለቱን እንደሚያስታርቅ ገልጸዋል ።

አቶ ሸምሰዲን አህመድ ከክልል 5 እና አቶ ታደሰ ካሳ ከክልል 3 በቀረበው አስታራቂ ሀሳብ የተስማሙ ሲሆን " ማጠቃለያ ሀሳቡ ተስሉ ከተቀመጠ በኋላ 1 ድጋፍና 1 ተቃውሞ ቀርቦ ወደ ድምፅ ይኬዳል ። " የሚል አንቀጽ 15/1/ ሆኖ እንዲገባ የሚለውን ጉባኤው ተቀብሎታል ። የማጠቃለያ ሀሳቡ የግድ ከመድረኩ ብቻ መቅረብ እንደሌለበት በስብሰባው ተጠቁሟል ።

በሌላ በኩል አቶ ሀሰን ኢብራሂም ከክልል 5 ኢትዮጵያ በሕዝቦች ፈቃድ እንድትገነባ ጥረት በሚደረግበት በአሁኑ ሰዓት ከባድ ክርክር የሚያስነሱ ጉዳዮች በድምፅ ብልጫ ወስኖ ማለፍ ቅር ስለሚያሰኝ አከራካሪ የሆኑ ጉዳዮች በድምፅ ብልጫ ሳይሆን በኮንሴንሰስ ወይም ኮምፖርማይዝ መወሰን እንደሚገባው አሳስበዋል ።

ሊቀመንበሩ ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ኮንሴንሰስ ወይም ኮምፖርማይዝ የጠፋ እንደሆነ ምን ማድረግ እንደሚቻል ጠይቀው በመቅረብ ላይ ያለው ለአናሳዎች ልዩ መብት /Affirmative Action/ ይሰጥ የሚል እንደሆነ አስተያየት እንዲሰጥበት ጋብዘዋል ።

በዚህም መሠረት አቶ ገለሱ ስልጢ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል የሕገ መንግሥት ጉባኤ በተሰጠው ኃላፊነት ሕገ መንግሥቱን በአብላጫ ድምፅ ሥርዓት አፅድቆ መሄድ እንጂ ከጉባኤው ውጭ ለሆነ ለወረዳ ፣ ለዞን ወይም ለክልል ያልተወሰነ ጉዳይን አሳልፎ መስጠት እንደማይገባ አሳስበዋል ።

ቀጥሎም አቶ አለማየሁ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ይህንኑ በመደገፍ የሚፀድቀው ሕገ መንግሥት ለኢትዮጵያ መገንቢያ ከመሆኑ አንፃር ጉባኤው የሚያሳልፋቸው ውሳኔዎች በተቻለ መጠን የሁሉንም ፍላጎት የሚያስማሙ ቢሆኑ እንደሚመረጥ ፣ ሆኖም ጉባኤተኛው በሙሉ አንድ ዓይነት አስተሳሰብና ፍላጎት ሊኖረው ስለማይችል በድምፅ ብልጫ ካልተወሰነ ያለመስማማት ችግር እንደሚፈጠር በመሆኑም የክልሎች የብሔር ብሔረሰቦችና አናሳ ሕዝቦች መብቶች በሕገ መንግሥቱ ብቻ ሳይሆን በወረዳ ፣ በዞንና በክልል በሚወጡ ዝርዝር ሕጎች እንደሚከበሩ ተገንዝቦ ሕገ መንግሥቱ በአብላጫ ድምፅ ወስኖ ማለፍ እንደሚመረጥ ገልጸዋል ።

ቀጥሎም አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 በበኩላቸው በአሁኑ ሰዓት ጥረት በመደረግ ላይ ያለው ያለፈውን የታሪክ ገጽታ አስወግዶ አገሪቱን በአዲስ

ምንም እንኳን የሕገ መንግሥት አቅጣጫ ለመምራት መሆኑ አጠያያቂ እንዳልሆነ ፣ የአካባቢያቸው ተወካዮች ጉባኤ አባላት በጥቅሉ ሲታይ የሕዝብ ተወካዮች ቢሆኑም በድምፅ ብልጫ ብቻ ሲወሰን መሆናቸውን በዚህ ሁኔታ የአጠቃላዩ ፍላጎት እየታየ ፣ ይህንን ችግር የአካባቢው ሕዝብ ፍላጎት ያለመታየት ችግር እንደሚያጋጥመው እንደ ዋና የአሠራር ደግሞ እንዲሁ ማለፍ ስለማይቻል በአብላጫ ድምፅ መወሰንን የአንድ ክልል ተወካዮች መንገድ መውሰድና ለዚህም መንገድ የተወሰነውን ግን የማድረግ ከግማሽ በላይ ሆነው እንደገና እንዲታይላቸው ከጠየቁ እንዲታይላቸው ዕድል ቢከፈት የዚህ ዓይነት ጥያቄ የሚያቀርቡት ከጠቅላላው የጉባኤ አባላት አንፃር

ሲታይ ጥቂት ስለሚሆኑ ችግር እንዳያመጣ አሳስበዋል ::

አቶ ሀሰን ኢብራሂም ከክልል 5 በቤቱ የሚደረገው ስምምነት ከሁሉም ወገን የመነጨ እንደሆነ በአብላጫ የተወሰነው እንደገና እንዲታይ ከተፈቀደ ጉባኤው ለአናሳው ወገን የሰጠውን ግምት ስለሚያሳይ የቀረበውን ሀሳብ እንደሚቀበሉት አመልክተዋል ::

በማስከተልም ከክልል 5 አንድ የጉባኤ አባል የግለሰቦች ሀሳብ ማፈን ተገቢ ስላልሆነ አንድ ሰው ሀሳብ ሲያቀርብ ሀሳቡን እስከ መጨረሻው ሊገፋበት እንደሚገባና ስምምነት ላይ ያልተደረሰባቸው ጉዳዮችን በተመለከተ የአንድ ክልል ተወካይ ሲጠይቁ ራሳቸው ተወያይተው ያቅርቡ እንጂ ውሳኔው ለቤቱ መሆን እንደሌለበት ገልጸዋል ::

በሌላ በኩል ደግሞ ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ከክልል 5 የጉባኤው አባላት ከአንድ ክልል የመጡት ሁሉ አንድ ዓይነት አቋም ይዘው ይመጣሉ ማለት እንደማይቻል ፣ ተወክለው የመጡት የግል ወይም የፖለቲካ ድርጅቶችን አላማ ይዘው ስለሆነ በዚህ ረገድ ውሳኔ በክልል ወይም በብሔረሰብ ሲባል ችግር እንደሚያመጣ ፣ ለምሳሌ ሁለት ሁለት ተወካዮች ካሉባቸው የድሬዳዋ ልዩ ክልል ወይም ከክልል 13 ከመጡት አንዱ ውሳኔው እንደገና ይታይልኝ ቢሉ 525 ሰው በድምፅ የወሰነውን እንደገና መገልበጥ እንደሚሆን ፣ ይህ ሲታይም ለአናሳዎች ይጠቅማል ተብሎ ከግማሽ በላይ የክልል ተወካዮች ውሳኔ እንደገና እንዲታይላቸው የሚለው በአሠራር ላይ ችግር እንደሚኖረው ፣ በድምፅ ብልጫ የሚለው አሠራርም የክልል 5 የተወካዮች ይዘውት የመጡት አቋም መሆኑን በራሳቸውና በኢትዮጵያ ሶማሌ ዲሞክራሲያዊ ሊግ ስም ተናግረዋል ::

ከዚያም አቶ አባየ ፀሐዬ ከክልል 1 በዲሞክራሲያዊ አሠራር ቀላሉና ትክክለኛው የአብላጫ ድምፅ ውሳኔ እንደሆነ ፣ ሆኖም ከአንድ አካባቢ የመጡና ውይይት የሚደረግበት ጉዳይ የሚያሳስባቸው ሆኖ ነገር ግን ጉዳዩ ለጊዜው ግልጽ ባይሆንላቸውና ወዲያውኑ ለመወሰን የሚያስቸግር ቢሆን ተጨማሪ ጊዜ ሰጥቶ



በጉዳዩ ላይ ከተወያዩ በኋላ እንደገና እንዲታይላቸው ሲጠይቁ መፍቀዱ የወከሉትን ሕዝብ ለማሳመን እንደሚረዳ አብራርተዋል ::

አያይዘውም ስለአንድ ክልል ሲወሳ ማየት የሚገባው ተወካዮች 1 ወይም 2 መሆናቸውን ሳይሆን የወከላቸውን ሕዝብ ስለሆነና እንደገና ይታይልን የሚለውን ጥያቄ ማስተናገዱም ይህን መሰል አጀንዳዎች በጣም ጥቂት ሊሆኑ ከመቻላቸው አንፃር ጉባኤውን የሚጠይቀው ነገር ቢኖር ጊዜ ብቻ እንደሆነ ፣ብዙ ዓይነት ሕዝቦችና የተለያዩ አመለካከቶች በሚገኙባት አገር ውስጥ የቻሉትን ያህል በሕዝቦች መካከል መተማመን ለመፍጠር ዋናው አሠራር የአብላጫ ድምፅ ሆኖ በልዩ ሁኔታ ግን እንደገና የማየት ዕድልን ክፍት ማድረግ እንደሚገባ ፣ ይህ ሲባልም ሙሉ በሙሉ መተማመንን ያመጣል ማለት እንዳልሆነ አመልክተዋል ::

ቀጥሎም አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 በአቶ አባይ ፀሐዬ የቀረበውን ሀሳብ በመደገፍ በአንድ ጉዳይ ላይ ውሳኔ ከተሰጠ በኋላ የአንድ ክልል ተወካዮች ተወያይተው እንደገና እንዲታይላቸው ሲጠይቁ ዕድሉን መስጠት ጉባኤው ለክልሎች ሊሰጣቸው ከሚገባቸው መብቶች እጅግ ዝቅተኛው እንደሆነ ፣ ጉዳዩ እንደገና እንዲታይላቸው የሚጠይቁት ክልሎች ተወካዮች ማነስ ይህንን ዕድል ላለማግኘት ምክንያት ሆኖ መቅረብ እንደማይገባው ፣ ለምሳሌ ከክልል 13 ፣ 3 ተወካዮች መካከል አንዱ ውሳኔው እንደገና እንዲታይለት ቢጠይቅ የጠያቂው አንድ መሆን ሳይሆን የወከለውን ሕዝብ ከግምት ውስጥ በማስገባት ጥያቄውን መቀበሉ ጉባኤው ለወካዩ ሕዝብ የሰጠውን ክብር ከማመልከት በስተቀር ችግር እንደማይኖረው ፣በዚህ ሁኔታ የቀረበውን ጥያቄ የተቻለውን ያህል ተጨማሪ ጥረት አድርጎ ለማሳመን መሞከር በመጨረሻ ግን በዋናው የአሠራር መንገድ በአብላጫ ድምፅ ጉዳዮችን መወሰን እንደሚጠቅም ገልጸዋል ::

ከዚያም ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ከክልል 5 ውሳኔ በብሔር/ ብሔረሰብ ወይም በክልሎች ጥያቄ እንደገና መታየት እንደሌለበትና ይህም የሕዝቦችን መብት እንዲታፈን ከመፈለግ ሳይሆን እንደገና ይታይልኝ የሚለው ጥያቄ የሚያሳይ ይሆናል በሚል ግምት ውስጠ ደንቡ ውስጥ ማስቀመጥ የማይገባ መሆኑን በማሰብና የብሔር/ብሔረሰቦችና የክልሎች ጥያቄ ተደባልቆ መታየት ስለሌለበት እንደሆነ አስገንዝበዋል ::

አያይዘውም ለጉባኤው የተወከሉ ጉባኤተኞች በግልም በፖለቲካ ድርጅትም ተወክለው ሲመጡ የየግላቸው የፖለቲካ አመለካከት ወይም የየድርጅቶቻቸው የፖለቲካ መስምር ይዘው እንጂ አንድ ወጥ የሆነ የአንድ ክልል አቋም ስላልሆነ ከግማሽ በላይ የክልሉ ተወካዮች በሚያቀርቡት ጥያቄ ውሳኔ እንደገና ይታይ የሚለውን ማስተናገድ አስቸጋሪ እንደሚሆን ገልጸዋል ::

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ አንቀጽ 15ን በተመለከተ የሚደረገው ውይይት የበለጠ መብላላት እንደሚገባውና ዕለቱም አርብ ስለሆነ የእስልምና ሃይማኖት ተከታዮች የመስገጃ ጊዜ ለመስጠት ውይይቱ ቆሞ ከቀኑ 9.00 ሰዓት እንደሚቀጥል አስታውቀው ጉባኤው ለሻይ ዕረፍት ተነስቷል ::

ከሰዓት በኋላም ጉባኤው ውይይቱን በአንቀጽ 15 ላይ ከመጀመሩ በፊት በጉባኤው 505 የሕገ መንግሥት ጉባኤ አባላት እንደተገኙ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አስታውቀዋል ::

ጉባኤው ወይይቱን በ9:10 ሰዓት ላይ በአንቀጽ 15 በመጀመር ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ከክልል 5 ጉባኤው በሚቱ ሰብሰባው በአንቀጽ 15 ንዑስ አንቀጽ 1 ላይ ባደረገው ውይይት የጉባኤው ውሳኔ የአንድን ክልል ሕዝብ ወይም ብሔር / ብሔረሰብ የሚነካ ከሆነና ከክልሉ ሕዝብ ተወካዮች ከግማሽ በላይ የሆኑት ወሳኔው እንደገና እንዲታይላቸው ከጠየቁ ጉባኤው ጉዳዩን እንደገና እንዲያየው እንዲደረግ ሀሳብ መቅረቡን ጠቁመው ይህ ሀሳብ የጉባኤውን አላማ ወደ ኋላ የሚጎትት ፣ የብሔር ብሔረሰቦችን በፈቃደኝነት አብሮ መኖር የሚያስት ፣ በሕዝቦች መካከል ምንም ዓይነት መተሳሰር የለም ወደሚል አቅጣጫ የሚያመራ እንደሆነ አብራርተዋል ::

በሌላ በኩል ደግሞ አቶ ዩሱፍ መሐመድ ከክልል 2 ጉባኤው ከብዙ ብሔር ብሔረሰቦች የተዋቀረ እንደሆንና የሚያስተላልፋቸውም ውሳኔዎች አናሳ ብሔር ብሔረሰቦችን ይበድላሉ ብለው እንደማያምኑ ጠቁመው በውሳኔዎች ቅሬታ ያላቸው የክልል ወይም የብሔር ብሔረሰቦች ተወካዮች ውሳኔዎች እንደገና እንዲታዩላቸው የማቅረብ መብት መፍቀድ ጉባኤው ለሕዝቡ በተለይም ለአናሳ ብሔር ብሔረሰቦች ያለውን ከበሬታ እንደሚያመለክት ገልጸዋል ::

ቀጥሎም አቶ ማርቆስ ልዕላንጎ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ጉባኤው ማናቸውንም ውሳኔዎች ለተወሰኑ ክልሎች ወይም ብሔር ብሔረሰቦች ተወካዮች የሚተው ባለመሆኑ የብሔር/ብሔረሰቦች ወይም ሕዝቦች መብት የሚነኩ ውሳኔዎች እንደገና እንዲታዩ በክልሉ ተወካዮች አብላጫ ድምፅ ከተጠየቀ መታየት እንዳለበት አሳስበዋል ::

ከዚያም የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ የጉባኤው አባላት የወከላቸውን ሕዝብ ፍላጎት እንዲገልጹና ሕገ መንግሥቱን በዲሞክራሲያዊ መንገድ ለማርቀቅ እንዲችሉ ቤቱ ከተቀበላቸው ሌሎች የደንቡ አንቀጾች አንቀጽ 15 ንዑስ አንቀጽ 1 እንደማይለይ ፣ ሆኖም ግን የክልሉ ተወካዮች ሀሳባቸውን ለመግለጽና



የሕዝባቸውን ፍላጎት እንደገና ለማቅረብ የበለጠ ዋስትና ለመስጠትና በግልጽም ለማስቀመጥ አንቀጽ 15 ንዑስ አንቀጽ 1 ፣

ሀ. ጉባኤው ወደ ውሳኔ ከመድረሱ በፊት የክልሎችን ወይም የብሔር የብሔረሰቦችን መብት ሊነካ በሚችል ጉዳይ ላይ ሰፊና ጥልቅ ውይይት እንዲደረግበት ያደርጋል ::

ለ. ከሰፊና ጥልቅ ውይይት በኋላ ውሳኔ ተሰጥቶበት የአንድ ክልል ሕዝቦች ወይም የብሔር / ብሔረሰቦች መብት የሚነካ ከሆነ ለዳግም ውሳኔ በክልል ወይም ብሔር / ብሔረሰብ ተወካዮች አብላጫ ድምፅ ሊጠየቅ ይችላል::

በመጨረሻም ጉዳዩ በጉባኤው ድምፅ ብልጫ ይወሰናል የሚል ሀሳብ በንዑስ አንቀጹ እንዲታከል ሀሳብ አቅርበዋል ::

በሌላ በኩል ደግሞ አቶ ሙሉጌታ ገ/ሕይወት ከክልል 1 ጉባኤው የሰጠውን ውሳኔ በ2/3ኛ ድምፅ መሻር እንደሚቻል በደንቡ ከተቀመጠ ሌላ የአንድ ክልል ሕዝቦች ወይም ብሔር/ብሔረሰቦች መብት ሊነኩ የሚችሉ ውሳኔዎች ቅሬታ ከቀረበባቸው እንደገና ሊታዩ እንደሚችሉ ማስቀመጡ ጉባኤው ሁለት ዓይነት ውሳኔ ማለትም የተወሰነን ጉዳይ እንደገና የማያ ሥርዓት እንዲኖሩት ያደርጋል የሚል አስተያየት የሰነዘሩ ሲሆን ለዚህም ከጉባኤው ሊቀመንበር ከዶ/ር ነጋሲ ጊዳዳ በተሰጠው ምላሽ በአንቀጽ 15 ንዑስ አንቀጽ 1 ውሳኔ የመመለሻ ሥርዓት የክልሎችን ወይም የብሔር ብሔረሰቦችና ሕዝቦች መብት ለሚነኩ ጉዳዮች በልዩ ሁኔታ እንደሚታይ ፣ በአንቀጽ 15 ንዑስ አንቀጽ 4 ለሌሎች የጉባኤው ውሳኔዎች እንደገና የሚታዩበት በአጠቃላይ ከጉባኤው አባላት አብላጫ ድምፅ ሲወሰን እንደሆነ አስረድተዋል ::

በመጨረሻም በጉዳዩ ላይ በበቂ ሁኔታ ቤቱ መወያየቱ ተገልጾ በድምፅ እንዲወሰን በከፍተኛ የጉባኤ አባላት በመደገፉ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ በአንቀጽ 15 ንዑስ አንቀጽ 1 ላይ እንዲታከል ያቀረቡት የማሻሻያ ሀሳብ ለድምፅ ቀረቦ 485 የድጋፍ ፣ 5 የተቃውሞና 22 የድምፀ ተአቅቦ በመመዝገቡ ማሻሻያው ተቀባይነት አግኝቷል ::

ከዚያም ጉባኤው በሌሎች የአንቀጽ 5 ንዑስ አንቀጾች ውይይቱ የቀጠለ ሲሆን ከላይ በአንቀጽ 5 ንዑስ አንቀጹ 1 የተሰጠው ውሳኔ በዚህ አንቀጽ ንዑስ አንቀጽ 4 ከተጠቀሰው ሀሳብ ጋር ያለው ልዩነት ምን እንደሆነ እንዲብራራላቸው አቶ ተፈራ መስቀሌ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ጥያቄ ስላቀረቡ አንቀጽ 15 ንዑስ አንቀጽ 1 የክልሎችን ወይም የብሔር / ብሔረሰቦችን መብት የሚነኩ ውሳኔዎች

እንደገና ለማየት የሚያስችል መሆኑን ፣ በዚህ አንቀጽ ንዑስ አንቀጽ 4 ሌሎች ውሳኔዎች በማንኛውም የጉባኤ አባል ጥያቄ እንደገና እንዲታይ በጉባኤው አባላት አብላጫ ድምፅ መደገፍ እንዳለበት የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ ምላሽ ሰተዋል ።

ቀጥሎም ዶ/ር አረጋዊ አክሊሉ ከክልል 1 ጉባኤው የሚያደርጋቸው ውይይቶች ግልጽ መሆን እንዳለባቸው እንደሚያምኑና ከዚህ በኋላም ምንም ምርጫ እንደማይደረግ ገልጸው በአንቀጽ 5 ንዑስ አንቀጽ 2 " ጉባኤው እንደየሁኔታው ድምፅ አሰጣጡ በግልጽ እጅ በማውጣት ወይም በሚስጥር እንዲሆን ያደርጋል ፡፡ በሚል ለምን እንደተቀመጠ እንዲብራራላቸው ጠይቀው የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ አንዳንድ ውሳኔዎች በሚስጥር ድምፅ አሰጣጥ ሂደት ጉባኤው ሊያስተላልፍ እንደሚችል እንዲሁም ወደፊት የሚደረጉ ምርጫዎች የሉም እንዳልተባለ ገልጸው የአንቀጹ መቀመጥ እንደማይጎዳይ አመልክተዋል ።

አቶ ቴዎድሮስ በካፋ ከክልል 3 የዛሬ ወሳነው ውሳኔ ነገ ከሚያያቸው ጉዳዮች ጋር የተያያዘ እንደሆነ ገልጸው ውሳኔው በመቃወም በአንቀጽ 15 ንዑስ አንቀጽ 1 መሠረት እንደገና ማቅረብ የሚችሉት ውሳኔው ከተሰጠ ከምን ያህል ጊዜ በኋላ እንደሆን እንዲወሰን ጠይቀዋል ።

ለዚህም በውሳኔው ላይ እንደገና ለመወያየት በአንቀጽ 5 /ሐ/ ላይ እንደተቀመጠው በ2/3ኛ ድምፅ መደገፍ እንዳለበት ፣ በአንቀጽ 15 ንዑስ አንቀጽ 1 የክልል ሕዝቦች ወይም ብሔር/ብሔረሰቦችን የሚነኩ ውሳኔዎችን እንደገና ለማየት ከክልሉ ተወካዮች በአብላጫ ድምፅ ከቀረበ በልዩ ሁኔታ እንደሚታይ ፣ በአንቀጽ 15 ንዑስ አንቀጽ 4 ላይ ውሳኔው እንደገና እንዲታይ ከጉባኤው አባላት በአብላጫ ድምፅ ከተወሰነ ጉዳዩ በድጋሚ ለውይይት እንደሚቀርብ ከተለያዩ የጉባኤ አባላትና ከመድረኩ ማብራሪያ ተሰጥቶ ጊዜው ግን እንዲወሰን ሀሳቦች ቀርበዋል ።

አቶ አሊ አብዶ ከክልል 14 የክልሎች ወይም የብሔር/ብሔረሰቦችን መብት የሚነኩ ውሳኔዎች እንደገና እንዲታይ ከተጠየቀ ዳግም ውሳኔውን ለመሻር የሚቻለው በአብላጫ ድምፅ ነው ወይንስ በ2/3ኛ ድምፅ ነው የሚል ጥያቄ አቅርበው የጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ዳግም ውሳኔው እንደሌሎች የጉባኤው ውሳኔዎች በአብላጫ ድምፅ እንደሚተላለፍ ምላሽ ሰተዋል ።

ከዚያም ጉባኤው ውሳኔው እንደገና እንዲታይ የሚቀርብ ጥያቄ ውሳኔው ከተሰጠ ከምን ያህል ጊዜ በኋላ ሊቀርብ ይችላል በሚለው በአቶ ቴዎድሮስ በካፋ ከክልል 3 በቀረበው ጥያቄ ላይ ወይይቱን የቀጠለ ሲሆን አቶ መሀሙድ ድሪር ከክልል 5 በሰጡት አስተያየት በተለይ የክልሎች ወይም የብሔር / ብሔሰቦችን



መብት የሚነኩ ውሳኔዎች እንደገና እንዲታይ የሚቀርብ ጥያቄ ጉባኤው ሕገ መንግሥቱ ማርቀቁን እስኪያጠናቅቅ ድረስ ሊስተናገድ እንደሚገባ ገልፀዋል።

በሌላ በኩል ደግሞ ጉባኤው የሕገ መንግሥቱን አንቀጾች በማፅደቅ ሂደት ከገፋ በኋላ ውሳኔ ያሳለፈባቸው ጉዳዮች እንደገና እንዲታዩ ከቀረቡ የጉባኤው ሂደት እንደገና ወደ ኋላ የሚመልሱ በመሆናቸውና የአንዱ ውሳኔ መሻር ሌላውንም ስለሚያበላሽ ጉዳዩ እንደገና እንዲታይ በፓርላሜንታሪ አሠራር የተለመደው የ24 ሰዓት ጊዜ ገደብ እንደሆነ ፣ የጉባኤው ውሳኔ የአንድን ክልል ወይም ብሔር / ብሔረሰብ መብት የሚነካ መሆን አለመሆኑን ለመገምገም 24 ሰዓት እንደሚበቃ አቶ አሰፋው ቀኖ ከክልል 4 ፣ ዶ/ር ተከተል ፎርሲዶ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ፣ አቶ ሐሰን አህመድ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ፣ አቶ ሸምሰዲን አህመድ ከክልል 5 ፣ አቶ አሊ አብዶ ከክልል 14 አስተያየት ሰንዝረዋል ።

በሌላ በኩል ውሳኔው ከተላለፈ በኋላ ከሚለው ዐረፍተ ነገር ቀጥሎ በሚካሄደው የስብሰባ ቀን የሚሉ ሀሳቦች ከተለያዩ ተወካዮች ቀርቦ በመጨረሻ ውሳኔ እንደገና እንዲታይ የሚቀርብ ጥያቄ በአንቀጽ 15 ንዑስ አንቀጽ 4 ከመጀመሪያው ዐረፍተ ነገር ቀጥሎ " በልዩ ሁኔታ ጉባኤው ካልወሰነ በስተቀር ውሳኔውን እንደገና ለማየት በሚቀጥለው ስብሰባ ጥያቄው መቅረብ አለበት ፡፡ " የሚል ዐረፍተ ነገር እንዲታከል የጉባኤው ሊቀመንበር ያቀረቡትን ሀሳብ ቤቱ ተቀብሎታል ።

ቀጥሎም የክልሎችን ወይም የብሔር / ብሔረሰቦችን መብት የሚነኩ ውሳኔዎች እንደገና እንዲታዩ ስንት ጊዜ ሊጠየቅ ይችላል የሚል ጥያቄ አቶ አሊ አብዶ ከክልል 14 ጥያቄ አቅርበው የጉባኤው ሊቀመንበር እነዚህ ጉዳዮች የመጀመሪያ ውሳኔያቸውን ከማግኘታቸው በፊት ጥልቅና ሰፊ ውይይት እንደሚደረግባቸው ፣ እንዲሁም ሆኖ ውሳኔ ከተሰጠባቸው በኋላ እንደገና እንዲታዩ ከተጠየቀ ሊስተናገዱ የሚችሉበት አንድ ጊዜ ብቻ እንደሆነ አብራርተዋል ።

የጉባኤው ዋና ፀሐፊም ከዚሁ ጋር በማያያዝ በአንድ ጉዳይ ላይ ውሳኔው እንደገና ይታልኝ የሚል ጥያቄ አንድ ጊዜ ብቻ እንደሚቀርብ ፣ ይህም በአንቀጽ 15 ንዑስ አንቀጽ 4 ላይ በውስጠ ታዋቂነት እንደተቀመጠ ፣ ሆኖም ያልረባ ጉዳይ እየተደጋገመ በመቅረብ የጉባኤውን ሂደት የሚያጓትት ከሆነ በስብሰባ ሥነ ሥርዓት መክልከል እንደሚቻል አሳስበዋል ።

ከዚያም በአንቀጽ 15 ንዑስ አንቀጽ 5 ላይ አንድ የጉባኤ አባል በስብሰባ ወቅት ድምፀ ተአቅቦ ያደረገበትን ምክንያት ወዲያውኑ ለጉባኤው በቃል ሊገልጽ የሚችልበት በግልጽ ካልተቀመጠ በስተቀር " ሊቀመንበሩ ድምፀ ተአቅቦ ያደረጉትን

ምክንያታቸውን ለፀሐፊው እንዲያቀርቡ ሊያዝ ይችላል ። " ድምፀ ተአቅቦ ወዲያውኑ የመግለጹን መብት ሊያግድ ይችላል የሚል ሀሳብ አቶ አዳሙ ደገፉ ከክልል 14 ስላቀረቡ ንዑስ አንቀጹ በጠየቁት መሠረት እንደሚስተካከል የጉባኤው ሊቀመንበር አመክልተዋል ።

ቀጥሎም ጉባኤው በአንቀጽ 16 ላይ ውይይቱን የቀጠለ ሲሆን ማንኛው ሕግ ፍፁም ሊሆን እንደማይችል አቶ መኩሪያ ታፈስ ከክልል 14 ገልጸው በስውጠ ደንቡ ያልተጠቀሱ ግን የጉባኤውን የውይይት ሥነ ሥርዓት የሚመለከቱ ጉዳዮች ቢነሱ ተፈጻሚነታቸው በፓርላማ አሠራር ደንብ መሠረት እንደሆነ የሚገልጽ ማሟያ ንዑስ አንቀጽ ሊቀረጽ ይገባል የሚል ሀሳብ አቅርበዋል ።

በሌላ በኩል አቶ መሐመድ አህመድ ከክልል 5 ደንቡ የሚፀድቀው በአብላጫ ድምፅ በመሆኑ መሻሻል ያለበት ከአብላጫ ድምፅ ከፍ ባለ ድምፅ ሊሆን ስለሚገባ በ2/3ኛ ድምፅ ሊሻሻል ይችላል ተብሎ አንቀጹ እንዲሻሻል ሀሳብ አቅርበዋል ።

ቀጥሎም አቶ ሸምሰዲን አህመድ ከክልል 5 በደንቡ ተፈጻሚ ሊሆኑ የማይችሉ ጉዳዮች ደንቡን በማሻሻል ሊስተናገዱ ስለማይችሉ በፓርላማ አሠራር ደንብ መሠረት ተፈጻሚ እንደሚሆኑ የሚገልጽ ንዑስ አንቀጽ በአንቀጹ ውስጥ መጥቀስ አስፈላጊ እንደሆነ ገልጸዋል ።

ከዚያም አንቀጽ 16 " በደንቡ ተፈጻሚ ሊሆኑ የማይችሉ ጉዳዮች በፓርላማ አሠራር ደንብ መሠረት ተፈጻሚ ይሆናሉ ። " ተብሎ እንዲቀመጥ የቀረበው ሀሳብ ለድምፅ ቀርቦ በአንድ ድምፅ ሲደገፍ በአብዛኛው የጉባኤው አባላት ተቃውሞ ስለገጠመው ውድቅ ሆኗል ።

በሌላ በኩል አንቀጽ 16 ደንቡ በ2/3ኛ ድምፅ ሳይሆን በአብላጫው ድምፅ ሊሻሻል ይችላል የሚለው ሀሳብ ከሁለት ተቃውሞ በስተቀር በአብዛኛው የጉባኤ አባላት ድጋፍ ተቀባይነት አግቷል ።

ከዚያም አንቀጽ 17 " ደንቡ ተዘጋጅቶ ለአባላት ከተሰራጨበት ጊዜ ጀምሮ ሥራ ላይ ይውላል ። " ተብሎ እንዲሟላ ቤቱ ተስማምቷል ። በመጨረሻም በአጠቃላይ የጉባኤው ውስጠ ደንብ እንዲፀድቅ ለድምፅ ቀርቦ ከአንድ ድምፀ ተአቅቦ በስተቀር በጉባኤው አባላት ተደግፎ ፀድቋል ።

ቀጥሎም ጉባኤው በቃለጉባኤ ቁጥር 3 ውይይቱን የቀጠለ ሲሆን የሚከተሉትን እርምቶችን አድርጓል ፣

በገጽ 5 ላይ ፣

. አቶ ወንድሙ ቱሮ ብሔረሰባቸው ከሌ ፣

. አቶ አቶ በሺር ሼክ ሰይድ ብሔረሰባቸው ሶማሌ ፣

. አቶ ሳህሌ ግራር ብሔረሰባቸው ኩናማ፣



አቶ አብዱራህማን አብዱልቃድር የሚለው ሐጂ አብዱራህማን አብዱልቃድር ተብሎ እንዲስተካከል ።

በገጽ 6 ላይ ፣

. ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ብሔረሰባቸው አማራ

. አቶ አብራሂም አህመድ ብሔረሰባቸው በርታ አባታቸው መሐመድ

. አቶ ዴቪድ ኡከዌር ብሔረሰባቸው አኝዋክ

ተብሎ እንዲስተካል ተደርጓል ።

አስከትለውም የጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ከማስተካከያው በመነሳት የጉባኤው አባላት በጉባኤው ወቅት ሲናገሩ ስማቸውንም ሆነ ሀሳባቸውን ግልጽ በሆነ መንገድ እንዲገልጹ ፣ ቃለጉባኤ አዘጋጆቻችም ሆነ ጋዜጠኞች በስብሰባ ወቅት የተነሱ ነጥቦችና የተናጋሪዎችን ስም በትክክል እንዲይዙ አሳስበው ቃለጉባኤ ቁጥር 3 ከነማሻሻያው እንዲፀድቅ ለድምፅ ቀርቦ በሙሉ ድምፅ ተቀባይነት አግኝቷል ።

ከዚያም አስተዳደራዊ ጉዳዮችን በተመለከተም ውይይት የቀጠለ ሲሆን በቅድሚያ የጉባኤው ምክትል ፀሐፊ አቶ አባተ ኪሾ በሰጡት ማብራሪያ ጉባኤው የራሱ አስተዳደር ሠራተኞች ሊኖሩት እንደሚገባ ፣ ለዚህም መቅጠር ጊዜ ስለሚፈጅ እስከአሁን የሕገ መንግሥት ኮሚሽንን ሥራ ሲያከናውኑ የቆዩት ልምድ ያላቸው ሠራተኞች የጉባኤው ሠራተኞች እንዲሆኑ ጉባኤው ዕውቅና እንዲሰጥ ፣ እንዲሁም የፀደቀውን ውስጠ ደንብ ተግባራዊ ለማድረግ የዲስፕሊን ኮሚቴ ማቋቋሙ አስፈላጊ እንደሆነ ፣ ይህንንም በምርጫ ማቋቋሙ ጊዜ ስለሚፈጅ እያንዳንዱ ክልል አንድ ተወካይ መርጦ እንዲያቀርብ የጉባኤው አመራር ሀሳብ ማቅረቡን ገልጸዋል ።

አያይዘውም የጉባኤው ፀሐፊ የሕገ መንግሥት ኮሚሽን ሠራተኞች የጉባኤው የሠራተኞች እንዲሆኑ ጉባኤው ዕውቅና መስጠት ተጨማሪ ሠራተኞችን መቅጠሩና ለሥራ በሚያመች መልኩ ማደራጀቱን እንደማይከለክል ፣ የዲስፕሊን ኮሚቴ አባላትም ከየክልሉ መወከላቸው የየክልሉቹን ጉዳይ ለማየት ከማስቻሉም በላይ ከዚህ በፊት በኮሚቴዎች ምርጫ ጉባኤው የተከተለውን የብሔር / ብሔረሰቦች ተወካዮች ስብጥር ሊያንፀባርቅ እንደሚችል ጠቁመዋል ።

ከዚያም ጉባኤው የሎጂስቲክ መረጃ ኮሚቴ ሊኖረው ይገባል የሚል ከአንድ የጉባኤ አባል ለተሰነዘረው አስተያየት የሎጂስቲክ መረጃ ጉዳይ በአስተዳደራዊ አደረጃጀት የሚጠቃለል በመሆኑ በሚቀጥለው ሳምንት በሚቀርበው አስተዳደራዊ መዋቅር ካልተጠቀሰ ያኔ ሊነሳ እንደሚችል የጉባኤው ሊቀመንበር አመልክተዋል ።

ቀጥሎም ቤቱ በጉባኤው አመራር አባላት በቀረቡት ሁለት ሀሳቦች በተወያየበት ወቅት እስከ አሁን ቃለጉባኤን በማስራጨቱ ፣ በምግብና መኝታ መስተንግዶ እንዲሁም በአበል ክፍያ በኩል የሕገ መንግሥት ኮሚሽን ሠራተኞች ለጉባኤው እንደሆነ ፣ የዲሲፕሊን ኮሚቴ አባላት ከየክልሉ መሳካት ያሳዩት ጥረት አርኪ እንደሆነ ፣ የዲስፕሊን ኮሚቴ አባላት ከየክልሉ መወከላቸው የብሔር / ብሔረሰቦችን ስብጥር የሚጠብቅ መሆኑ የቀረቡት ሀሳቦች ተቀባይነት ሊያገኙ እንደሚገባ ከተለያዩ አባላት አስተያየቶች ተሰንዝሮ ቤቱ ሀሳቦቹን በሙሉ ድምፅ ተቀብሏቸዋል ።

የጉባኤው ምክትል ፀሐፊ አቶ አበተ ኪሾ አስተዳደራዊ ጉዳዮችን በተመለከተ በሰጡት ተጨማሪ ማብራሪያ ብር 7,067,200.08 ለሕገ መንግሥት ጉባኤ ሥራማስኬጃ በተወካዮች ምክር ቤት መፀደቁን ፣ የገንዘቡ መጠን ካነሰም ተጨማሪ ሊጠየቅ እንደሚቻል ከሰነዱ ጋር የተያያዘው ደብዳቤ እንደሚገልጽ ፣ ከተፈቀደው ገንዘብ ውስጥ ጉባኤው ሥራ ከጀመረበት ቀን ጀምሮ ምን ያህሉ ወጪ እንደሆነ የሂሳብ ሪፖርት ገና እንዳልተዘጋጀ ፣ ሪፖርቱ ሲዘጋጅ ለጉባኤው ሊቀርብ እንደሚችል አብራተው ለጥቃቅን ወጪዎች መሸፈኛ ለእያንዳንዱ አባል በወር ብር 500 መፈቀዱን ገልጸዋል ።

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር ጉባኤው እስከ አሁን ለሥራው አመቺ የሆኑ መሥፈርቶች እያሟላ መቆየቱን በቀጣይ ስብሰባው ግን በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ወይይቱን እንደሚጀምር ፣ በመሆኑም አባላቱ የሕገ መንግሥት ኮሚሽን ረቂቅ ሕገ መንግሥቱን በሚመለከት ያዘጋጀውን አጭር ማብራሪያ በማንበብ ፣ በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ መግቢያና ጠቅላላ ድንጋጌዎች ተዘጋጅተው እንዲመጡ አሳስበው የኮሚቴዎች አባላት ከስብሰባው በኋላ እንዲተዋወቁ ሀሳብ ቢያቀርቡም የፀሎት ጊዜ መድረሱን ሐጂ አብዱራህማን አብዱልቃድር በማሳሰባቸው ትውውቁ ለሚቀጥለው ቀን ጧት ተላልፏል ።

የጉባኤው አባላት ከተለያዩ ብሔር/ብሔረሰቦች የተወከሉ እንደመሆናቸው መጠን በሽግግር መንግሥቱ ለውድድር ቀርቦ አሸናፊ የሆነውና ትምክህተኞች የሚጠሉትን መዝሙር የጉባኤው አባላት አጥንተው በየዕለቱ ጉባኤው ሲጀመርና ሲጠናቀቅ እንዲዘመር ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ከክልል 5 ሀሳብ ቢያቀርቡም ጉዳዩ በቀጣዩ ስብሰባ እንደሚታይ ሊቀመንበሩ ገልጸው የዕለቱ ስብሰባ ከምሽቱ 12:05 ሰዓት ላይ ተጠናቋል ።



ጥቅምት 28 ቀን 1987 ዓ.ም 03:00 ሰዓት በሕገ መንግሥት ጉባኤ አዳራሽ የተካሄደው የኢትዮጵያ የሕገመንግሥት ጉባኤ ጉባኤ የተመራው በጉባኤው ሊቀመንበር በዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ሲሆን በትድሚያ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ በዕለቱ የተገኙ የጉባኤ አባላት ብዛት 523 ስለሆነ ስብሰባውን መጀመር እንደሚቻል ባስታቁት መሠረት ውይይቱ ተጀምሯል ። የዕለቱ አጀንዳም ፣

1. የኢትዮጵያ ሕገ መንግሥት ጉባኤ ቃለጉባኤ ቁጥር 4 መርምሮ ማፅደቅ ፣
2. በኢትዮጵያ የሽግግር መንግሥት ተወካዮች ምክር ቤት በፀደቀው የኢትዮጵያ ሕገ መንግሥት ረቂቅ ላይ ውይይት ማካሄድ :

በመጀመሪያ ጉባኤው ቃለጉባኤ ቁጥር 4 ገጽ በገጽ የተመለከተው ሲሆን ሊመንበሩ በየገጹ የማሻሻያ ሀሳብ ካለ እንዲቀርብ በጠየቁት መሠረት ፣

-ገጽ 1 ወ/ሮ እንወይን ገ/መድህን የሚለው ፣ ወ/ሮ እንወይ ገ/መድህን ፣

ገጽ 2 አቶ ሐመድ አባው የሚለው አቶ ሐመድ አባውካይ ፣

ገጽ 3 አቶ አብዱራዛቅ መሐመድ ከክልል 12 የሚለው ከክልል 14 ፣

አቶ ሀመድ ዓሊ የሚለው ፣ አቶ ሰመዱ ዓሊ ፣

አቶ ካራቴ ቡሉ የመለው ፣ አቶ ካራቴ ጉሉ ፣

አቶ ጴጥሮስ ማርሱ ብሔረሰብ ቀቢና የሚለው ፣ብሔረሰብ ቤንች ፣

አቶ ተመሳ ብሩ ብሔረሰብ ጋሞ የሚለው ፣ ብሔረሰብ ዳውሮ ፣

በሚል እንዲስተካከል ።

ገጽ 4 አቶ ሽፈራው ገለታ ከደቡብ ክልል የሚለው፣ ከኮንታ ብሔረሰብ የሚል እንዲጨመርበት ፣

አቶ ዳተራ ዳራ የሚለው ከክልል 2 ፣ አቶ ኃይለ ሐለፎም ከክልል 14 ተብሎ እንዲስተካከል ፣

ገጽ 5 አቶ መሐመድ ሞድአዴ የሚለው ፣ አቶ አህመድ ሞዴአዱ ፣

አቶ ሰይድ ሬድዋን ከስልጤ ብሔረሰብ ፣

አቶ ኡጣይሌ ከዘይሴ ብሔረሰብ

አቶ ታምራት በየነ ከጌድኦ ብሔረሰብ

ተብሎ እንዲስተካከል ፣

ገጽ 6 አቶ ኒሃልጋች ዲንግ ከኑኤር ብሔረሰብ የሚለው ከኑዌር ብሔረሰብ ተብሎ እንዲታረም ፣

ገጽ 7 አቶ ዲላ ኢዳቦ የሚለው አቶ ዴላ ኢያሱ ፣
ገጽ 8 አቶ ቀኚያለው ሳሌ ከትረሺ ብሔረሰብ የሚለው ከደራሼ ብሔረሰብ፣
አቶ ማቲዎስ መንታም ከጠንበሮ ብሔረሰብ የሚለው ከጠምባሮ ብሔረሰብ ፣
ከሚኢት ብሔረሰብ የሚለው ከሚኢኒት ብሔረሰብ ፣
አቶ ፀጋዬ ገለታ ከሚኒት ብሔረሰብ የሚለው አቶ አለማ ምስግና ፣
አቶ አለማ ምስጋና የሚለው አቶ አሊ አብዶ ከክልል 5
አቶ አሊ አብዲ ከክልል14 የሚለው አቶ አሊ አብዲ ከክልል 5
በሚል እንዲስተካከል ተጠይቶ በቤቱ ተቀባይነት አግኝቷል ::

ቀጥሎም አንድ የክልል 5 ተወካይ ብዙዎቹ ከክልል አምስት የመጡ የጉባኤ አባላት አማርኛ ቋንቋ ማንበብ እንደማይችሉ ጠቁመው የጉባኤው ቃለጉባኤዎች ተወካዮቹ ወደሚያውቁት ቋንቋ እንዲተረጎሙ የጠየቁ ሲሆን በቃለጉባኤ ያኘነት የተመደቡት ሰዎች በአማርኛ ቋንቋ የሚያዘጋጁ እንደሆነ ፣ እንዲሁም ጉባኤው በአማርኛ ቋንቋ ስለሚካሄድ ቃለጉባኤውም የጉባኤውን ውይይት በማካተት በአማርኛ ቋንቋ እንደሚጻፍ ፣ ስለዚህ በቃለጉባኤዎች ላይ ውይይት ከመደረጉ በፊት ቃለጉባኤዎች ለአባላት ስለሚሰጡ አማርኛ ቋንቋን የሚያውቁ ከተለያዩ ክልሎች የአማርኛን ቋንቋ ለማያውቁ በትብብር በመተርጎም መረዳዳት ይሻላል እንጂ ቡጉባኤው ለሚሳተፉ የአማርኛ ቋንቋን ለማይገባቸው ብዙ ሰዎች ቃለጉባኤዎችን በየቋንቋቸው ተርጉሞ ለማቅረብ አስቸጋሪ እንደሆነ ሊቀመንበሩ አስረድተዋል ::

ከዚያም አንድ የጉባኤ አባል የዜና ማሰራጫዎች የጉባኤ አባልን ስምና ብሔረሰብ ስህተት በሆነ መንገድ ስለሚያስተላልፉ ተወካዩን ከወከለው ብሔረሰብ ጋር የሚያጋጭ ሁኔታ ሊከሰት እንደሚችል ሥጋታቸውን በመጠቆም ስህተቱ እንዲስተካከል የጠቀሱ ሲሆን እንዲሁም አቶ አበበ አበራ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል በተለይ የኮሚቴ አባላት በምርጫ ሂደቶች ፣ የምርጫው፣ የብሔረሰቦችና የክልሎች ተዋፅኦ በቃለጉባኤዎች በትክክል ቢሰፍርም መገናኛ ብዙሃን አብዛኞቹ በተዛባ መልኩ ስላስተላለፉ የሚቋቋመው የሕግ አገልግሎት አስተካክሎ በማስተላለፍ ስህተቶ እንዲታረሙ አስተያየት አቅርበዋል ::

ቀጥሎም የጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ከዚህ በፊት እንደተገለጸው የጉባኤው አባላት በጉባው ውስጥ በሚወያዩበት ወቅት ሃሳብ አቅራቢ አባል ራሱን ቢያስተዋውቅ ለቃለጉባኤ አዘጋጆችና ለጋዜጠኞች ግልጽ እንዲሆንላቸው ድምፁን ከፍ አድርጎ መናገር እንዳለበት ፣ በተለይ የጭቁን ብሔረሰብ ተወካዮች ወይም የብሔረሰቦችን ስም ከትምክህተኞች ወገን በትክክል ያለመጻፍ እንዳለ በመረዳት



ጋዜጠኞች ቢጠነቀቁ እንደሚሻል ፣ የጉባኤ አባላት ስምና ብሔረሰብ እንዲሁም ክልል በመዘርዘር ከምርጫ ኮሚሽን ተዘጋጅቶ በቀረበው ሰነድ ላይ ስህተት ካለው ወደ ቃለጉባኤ ፅሕፈቶች በመሄድ መስተካከል እንደሚቻል ፣ ሰነዱም ጋዜጠኞችና ቃለጉባኤ አዘጋጆች በትክክል ለመጻፍ እንደሚረዳቸው ፣ መገናኛ ብዙሃን በተዛባ መልኩ እንዳያስተላልፉ በተደጋጋሚ ማሳሰቢያ መስጠቱንና ትክክል ያልሆነ ተላልፎ ከሆነ እንደገና አስተካክለው የማስተላለፍ ግዴታ ስላለባቸው በትክክል ያልተላለፈው ምን እንደሆነ ቢጠቀስና የተስተካከለው በጽሕፈት ቤቱ በኩል ቢተላለፍ መገናኛ ብዙሃን ቀደም ሲል የተሳሳተውን አስተካክለው ለማስተላለፍ እንደሚችሉ አስረድተዋል ::

በመጨረሻም ቃለጉባኤ ቁጥር 4 ከማስተካከያዎቹ ጋር እንዲፀድቅ ለድምፅ ቀርቦ ከአንድ ድምፀ ተአቅቦ በስተቀር ያለምንም ተቃውሞ በጉባኤው አባላት ተደግፎ ፀድቋል ::

በማስከተልም የጉባኤው ምክትል ፀሐፊ አቶ አባተ ኪሾ የዲሲፕሊን ኮሚቴ አባላትን ክልሎች መርጠው እንዳቀረቡና አባላት ራሳቸው የሥራ ክፍፍል አድርገው ሥራቸውን ከዕለቱ ማለትም ከጥቅምት 28 ቀን 1987 ዓ.ም ጀምሮ እንደሚያካሂዱ በመጠቆም የኮሚቴውን አባላት ለቤቱ ለማስተዋወቅ ሲባል የስም ዝርዝራቸውን እንደሚከተለው አቅርበዋል ፣

1. አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1
2. አቶ ኡርባ አባሀብ ከክልል 3
3. አቶ አቡኔ መንገሻ ከክልል 3
4. አቶ ኃይሉ ገመዳ ከክልል 4
5. አቶ መሐመድ ሼክ መሐመድ ከክልል 5
6. አቶ ዊልያም አማሀያ ከክልል
7 አቶ ማርቆስ ዳሞ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል
8 አቶ ወይናቶ አበራ ከክልል 12
9 አቶ ኢብራሂም ዘካርያ ከክልል 13
10. አቶ ተስፋዬ ሻረው ከክልል 14
11. አቶ አህመድ ኡስማን ከድሬዳዋ ልዩ

ናቸው ::

ቀጥሎም የጉባኤው ሊቀመንበር ጉባኤው በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ላይ መወያየት እንደሚጀምር ጠቁመው ውይይቱ የሚካሄድበት ሁኔታና የተመረጡ የተለያዩ ኮሚቴዎች አባላት ሥራቸውን እንዴት እንደሚያከናውኑ አመራሩ

የተወያየበት ስለሆነ የታሰበውን የአሠራር ሂደት የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ እንዲገልጹ ጠይቀዋል ::

በዚህም መሠረት የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ የጉባኤው አባላት የሕገ መንግሥቱን መግቢያና የመጀመሪያውን ክፍል አንብበው እንዲመጡ ተብሎ እንደነበረ አስታውሰው በሕገ መንግሥቱ ላይ የሚደረገው ውይይት በምን መልኩ መሆን እንዳለበት የጉባኤው አመራር አካል ጥቅምት 27 እና 28/1987 ዓ.ም እንደደተወያየበት ፣ በመሆኑም በአመራሩ የታሰበው የተዋቀሩ ኮሚቴዎች በሰነዱ ውስጥ ያሉትን መሠረታዊ ጉዳዮችን በተመለከተ ከቤቱ ሆነ ከሌላ አቅጣጫ የሚነሱ ጥያቄዎችና ልዩነቶችን እየበሰሉና በጥልቀት እየተወያዩ ጉባኤው እንዲያየው ለማድረግ ሲሆን በሕገ መንግሥቱ መግቢያና በምዕራፍ አንድ ሥር ጠቅላላ ድንጋጌዎች በሚል የተጠቀሰውን ግን ለኮሚቴዎች ሳይመራ ከወዲሁ ጉባኤው ሊወያይበት እንደሚችል ፣ ሌሎች አንቀጾች ግን ኮሚቴዎች ከባለሙያ ጋር በመተጋገዝ ተከፋፍለው እንዲወያዩባቸው መታሰቡን አመልክተዋል ::

አያይዘውም መግቢያው የሕገ መንግሥቱን መሠረታዊ ሀሳቦችን አጠቃልሎ ስለሚገልጽ በሕገ መንግሥቱ ይዘት ገና በሚገባ ውይይት ሳይደረግ በግቢያው ላይ መወያየቱ ለአካሄድ አመቺ ስለማይሆን በመግቢያው ላይ መጨረሻ ለመወያየት ጠቅላላ ድንጋጌዎች ግን አጠቃላይ የሆኑ ነጥቦችን ስላላከተተ ውይይቱን በእሱ ላይ ለመጀመር እንደታሰበ ፣ በተጨማሪም ኮሚቴዎች ከቤቱም ሆነ ከሌላ አቅጣጫ የሚነሱትን አይተው ለመወያየት ጊዜ ሊኖራቸው ስለሚያስፈልግ በተለይ ቤቱ በድንጋጌዎቹ የሚወያይበት ጊዜ ከሰዓት በፊት እንዲሆንና ከሰዓት በኋላ ግን ኮሚቴዎች የራሳቸውን ሥራ የሚያከናውኑበት እንዲሆን መታሰቡን ፣ ይህም የታሰበበት ምክንያት የጊዜ አጠቃቀሙ ሂደት ተቋራጭነት እንዳይኖረውና ጉባኤው በራሱና በኮሚቴዎች አማካይነት ጉዳዮችን በጥልቀት ለመመልከት ጊዜ እንዲኖረው ለማድረግ መሆኑን አውስተው በመጨረሻም ከአመራሩ በቀረቡ ሀሳቦች ላይ ቤቱ አስተያየት እንዲሰጥበት ጠይቀዋል ::

በዚህም መሠረት አቶ ዮሴፍ ቦራ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ለረጅም ጊዜ የተሳበው ሥርዓት እንዲሁም አስተዳደሩ የጣለውን ተፅዕኖና ጠመዝማዛ ሂደት በአንክሮ መመልከት አዲሲቷን ኢትዮጵይን ለመመሥረትና ሰፊው የኢትዮጵያ ሕዝብ አዲስ ሕይወት ይዞ ለመንቀሳቀስ እንዲችል ጉባኤው የተጣለበትን አደራ በብቃት መወጣት እንዳለበት ፣ ከመድረኩ የቀረበው ሀሳብ ጉባኤተኛውም ሆነ ኮሚቴዎች በሕገ መንግሥቱ ለመወያየት ሰፊ ጊዜ እንደሚያገኙና ኮሚቴዎች ተጨባጭ ጉዳዮችን እያቀረቡ ቤቱ እያጠናከረና እያዳበረው እንዲሄድም በጣም ጠቃሚና አመቺ የአሠራር ሂደትን የሚፈጥር እንደሆነ ገልጸዋል ::



አስከትለውም አቶ አብዱልራዛቅ መሐመድ ከክልል 14 በመግቢያው ጠቅላላ የሰነዱን ይዘት መግለጽ ስላለበት ከድንጋጌው ጀምሮ እስከ መጨረሻው ምዕራፍ መሆኑን ጠቁመው እያንዳንዱን የሕገ መንግሥት ይዘት በሰፋት ተወያይቶ ውክልናን በአግባቡ መወጣት ቢያስፈልግም በተቻለ ፍጥነት መሥራት ስለሚያስፈልግ ጧት ለጠቅላላ ጉባኤ ፣ ከሰዓት በኋላ ደግሞ ለኮሚቴዎች ሥራ መመደብ አግባብ ሲሆን ከተወሰኑ ጊዜያት በኋላ ግን ሰፊውን ሥራ ለጉባኤው የሚሰጥበት ሁኔታ መታሰብ እንዳለበት በማሳሰብ በጠቅላላ መንደርደሪያነት የመድረኩን ሀሳብ እንደሚደገፍ አስታውቀዋል ::

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር ጉባኤው በጠቅላላ ድንጋጌዎች ላይ ተወያይቶ እስከሚጨርስ ጥቂት ቀናት ድረስ ከሰዓት በኋላ ባለው ጊዜ ኮሚቴዎች ከሰነዶች በተጨማሪ ከተለያዩ ሰዎች ግንዛቤ በማግኘት ለማዘጋጀት እንደሚችሉ ፣ ኮሚቴዎች ተዘጋጅተው ከጨረሱ በኋላ ግን ሰፊ ጊዜ በመስጠት የጉባኤውን ውይይት ማራዘም ስለማይፈለግ ከሰዓት በኋላ ለኮሚቴዎች የውይይት ጊዜ ተብሎ እንደማይመደብ አመልክተዋል ::

ቀጥሎም ሐጂ አብዱራህማን አብዱልቃድር ከክልል 13 ጉባኤው የሕገ መንግሥቱን መግቢያ መጨረሻ ላይ ሳይሆን አስቀድሞ መወያየት እንደሚገባና ከሰዓት በኋላ ኮሚቴዎች ዝግጅት የሚያደርጉበት ጊዜ ሆኖ የቀሩት የጉባኤ አባላት ማረፋቸው አስፈላጊ እንደሆነ ሀሳብ አቅርበዋል ::

ለዚህም የጉባኤው ሊቀመንበር ሲመልሱ ከሰዓት በኋላ ለኮሚቴዎች የዝግጅት ጊዜ ቢመደብም ሌሎች የጉባኤ አባላት በግልም ሆነ በቡድን በሕገ መንግሥቱ ላይ ለመወያየት ስለሚችሉ እንደ ዕረፍት እንደማይቆጠር አስገንዝበዋል ::

ከዚያም አቶ መሀሙድ ድሪር ከክልል 5 ከዚህ ቀደም የነበሩት ሕገ መንግሥታት የመጀመሪያው የስጦታ ሲሆን የፋሽስታዊ ደርግ ሥርዓት ደግሞ ከምስራቃውያን የተቀዳ ሆኖ በመግቢያነቱም ሆነ በይዘቱ የላብ አደሩን አምባገነንነት ለማረጋገጥ የሚል የይስሙላ ሕገ መንግሥት እንደነበረ አስታውሰው ጉባኤው የሕገ መንግሥቱን ይዘት በማወቅ ኮሚቴዎችን እንዳዋቀረና መግቢያው ግን የሕገ መንግሥቱን መሠረታዊ ሀሳቦች ብቻ ሳይሆን ቃልኪዳንም ያካተተ በመሆኑ ጉባኤው ለኢትዮጵያ ብሔር ብሔረሰቦችና ሕዝቦች ምን ዓይነት ሕገ መንግሥት ለማፅደቅ የመጣ እንደሆነ በቅድሚያ ማሳወቅ ስለሚያስፈልግ ቃል ኪዳንን ለማስቀደም እንዲቻል ከመግቢያው እንዲጀመር የሚል ሀሳብ አቅርበዋል ::

ቀጥሎም አቶ ተመስገን ማሞ ከክልል 14 በሥነ ጽሑፍ አካሄድ ብዙውን ጊዜ ጽሑፉ ከተቀነባበረ በኋላ መግቢያ ፣ መቅድም እንደሚዘጋጅ ጠቁመው የሕገ መንግሥቱ መግቢያ ግን ሁሉንም ይዘት ስላካተተ ውይይቱ በመግቢያው ቢጀመር ችግር እንደማይፈጥር ገልጸዋል ::

በሌላ በኩል አቶ ኩማ ደመቅሳ ከክልል 14 ኮሚቴዎች የተቋቋሙት እያንዳንዱ ጉዳይ በጉባኤውና በኮሚቴዎች ሰፊ ውይይት ተደርጎበት በልዩነት ደረጃ የሚቀመጡት ዕልባት እያገኙ ለመወሰን በመሆኑ ይህ ሁኔታ ሳይከናወን የሰነዱን አበይትና አከራካሪ ጉዳዮችን ባካተተው በመግቢያው ላይ ውይይት ቢጀመር ውይይቱ የተሟላ እንደማይሆን ፣ በሕገ መንግሥቱ አንቀጾች ላይ ጉባኤው ከተወያየና ከወሰነ በኋላ በመግቢያው ላይ መጨረሻ መወያየት እንደሚያስፈልግና ታሪካዊ ሰነዱ ለኢትዮጵያ ሕዝብ መብትና ጥቅም የሚያረጋግጥ መሆኑንም በዚያን ጊዜ ቃል መግባት እንደሚቻል አመልክተዋል ::

አስከትለውም ወ/ሮ ዕጌ አስፋው ከክልል 3 በቤቱ የሚነሱትን ጥያቄዎችን ወደ መደምደሚያ ለማድረስና ከተለያዩ ክፍሎች መረጃ ካስፈለገም ለማቅረብ እንዲቻል ኮሚቴዎች መዋቀራቸውና የኮሚቴዎች መዋቀር ግን የሀሳቦች መደምደሚያ እንዳልሆነ ጠቅሰው በመግቢያው ላይ ያሉት ነጥቦች ብዙ ሊያወያዩና ሊያከራክሩ ስለሚችሉ በያንዳንዱ ጉዳይ ላይ ውይይት ተካሂዶ መግቢያው መጨረሻ ላይ ቢታይ የሚል ሀሳብ አቅርበዋል ::

በሌላ በኩል አቶ አዳሙ ደገፉ ከክልል 14 መግቢያ ለአንድ ሰነድ መጀመሪያ እንጂ መጨረሻ ስላልሆነ ጉባኤው ውይይቱን በድንጋጌዎች ላይ ቢጀምር ሥራ አስፈጻሚው ጉባኤውን ተመልክቶት ጉባኤው ተመልሶ ሊወያይበት እንደሚችል ገልጸው የመግቢያው መጨረሻ ሆኖ በማሰሪያነት መታየት እንደማይቀበሉት አመልክተዋል ::

ቀጥሎም የጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ የኢትዮጵያ ሕዝብን ወክሎ የተገኘው ጉባኤ ሕገ መንግሥቱን ከምዕራፍ አንድ ጀምሮ እስከ መጨረሻው ድረስ ባሉት የተለያዩ ጉዳዮች ውይይትና ክርክር በማካሄድ ከተስማማ በኋላ በሕገ መንግሥቱ መስማማቱን በመግቢያው ላይ ቃለ መሀላ መግባት ይሻላል በሚል አመራሩ ስለተመለከተው እንጂ በመግቢያው ይዘቶች ላይ የሚካሄደው ውይይትን ወደ ኋላ ለማስቀረት እንዳልሆነ አብራርተዋል ::

ከዚያም አቶ መሀሙድ ድሪር ከክልል 5 ጉባኤው በቅድሚያ በመግቢያው ላይ እንዲስማማና በሌሎች ጉዳዮች ላይ ውይይቱን እንዲቀጥል ማድረጉ የነበረ ቢሆንም በይዘቶቹ ላይ በጥልቀት ወይይትና ክርክር ተካሂዶ በመጨረሻ ስምምነት ላይ ከተደረሰ በኋላ ለሥራ ቅልጥፍና ስለሚያመች ቃለ መሀላ በመጨረሻ መግባት



ስለሚቻል ውይይቱ ከመግቢያው እንዲጀመር አቅርበውት የነበረውን ሀሳብ ማንሳታቸውን ገልጸዋል ::

በማስከተልም ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 ሕገ መንግሥቱ ሕዝቡ ስላልተወያየበትና የሕዝቡንም ፍላጎት ስለማያንፀባርቅና ሰብአዊ መብትንም ስለሚነካ መሰረዝ አለበት በሚል አቋም የፀኑ መሆናቸውንና አቋማቸውን ጽፈው እንደሚሰጡ እንጂ ክርክር ውስጥ እንደማይገቡ አስታውቀዋል ::

የጉባኤው ሊቀመንበር ጉባኤው ውይይት ከጀመረ ጀምሮ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ጽሑፎች አሉኝ ፣ ሀሳቤን በፅሑፍ አቀርባለሁ ብለው ቢያስታውቁም በጉባኤው ውስጠ ደንብ መሠረት እስከ አሁን ምን ዓይነት ጽሑፍ እንዳላቀረቡ ፣ ጽሑፎች ካሏቸው ለቤቱ ጠቃሚ የሆኑ ሀሳቦች ሊኖርባቸው ስለሚችል ለኮሚቴዎች ማቅረብ እንደሚችሉ ፣ ከዚህ ውጭ ግን ጽሑፍ አለኝ ብለው የሚደጋግሙት ጊዜ ለመጨረስ ካልሆነ በስተቀር ጥቅም ስለሌለው እንዲያስቡበት አስገንዝበዋል ::

ቀጥሎም ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 ፣ 30 ገጽ ጽሑፍ እንዳላቸውና ሳይታላቸው ቀረ እንጂ የመጀመሪያውን 3 ገጽ አምጥተው እንደነበር ፣ እንዲሁም በፈለጉት መድረክ ላይ እንደሚያቀርቡ ስለጠቀሱ የጉባኤው ሊቀመንበር ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ በጉባኤው የሚናገሩትን ቤቱ እንደሚሰማቸውና ለመናገር ዕድል እንደሚሰጣቸው ፣ በጽሑፍ የሚያቀርቡት ሀሳብ ካለ በጉባኤው ውስጠ ደንብ መሠረት እንዲያቀርቡ አሳስበዋል ::

አያይዘውም የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ ማንኛውም የጉባኤው ተሳታፊ ሥርዓት ጠብቆ በአጀንዳው መሠረት ሀሳቡን የመግለጽ መብት እንዳለውና ቀደም ሲል ጉባኤው ባፀደቀው ውስጠ ደንብ መሠረት በአንድ አጀንዳ ላይ ውሳኔ ከተላለፈበት በኋላ ተመልሶ መነሳት እንደሌለበት መጠቀሱን ፣ በመሆኑም በጉባኤው ውስጥ በማንኛው መልክ ማንም ከማንም በላይ ስላልሆነ ሁሉም አባል ለደንቡ ተገዥ መሆን እንዳለበት ፣ በአሁኑ ውይይት መግቢያውን አሁን እንወያይበት እና አንወያይበት /በመጨረሻ ላይ እንወያይበት/ የሚሉ ሁለት ሀሳቦች እንዳሉ ፣ ስለዚህም በሁለቱም ሀሳቦች ላይ በጥልቅ ውይይት አልተካሄደም ከተባለ ተጨማሪ የመናገር ዕድሎች በመስጠት ውይይቱ መቀጠል እንዳለበት ማሳሰቢያ አቅርበዋል ::

አስከትለውም የሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ሀሳብ በሕገ መንግሥቱ ላይ አንወያይበት የሚል መሆኑን ፣ ነገር ግን ጉባኤው በሕገ መንግሥቱ ላይ እንዲወያይበት ቀደም ሲል በድምፅ ብልጫ መደገፉን ፣ ስለዚህ ቤቱ ከሚነጋገርበት አጀንዳ ውጭ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ በፈለጉት መንገድ ጉባኤውን ሊወስዱት እንደማይችሉና ከአጀንዳ ውጭም ከአጀንዳ ጋር ባልተያያዘ ሲናገሩ ዝም

መባሉ ቀርቶ ሥርዓት መከተል እንዳለባቸው ፣ እስከ አሁን ድረስ ሀሳብ ሲያቀርቡ ጉባኤው ከሚወያይበት አጀንዳ ውጭ ለመግባት በመሞከር ቤቱ ተወያይቶ መደምደሚያ ላይ ሲደርስ መልሰው ሀሳቡን በማንሳት የቤቱን ውይይት በተደጋጋሚ ስለሚያንትቱ የቤቱን መብት እየተጋፉ መሆናቸውን ፣ ስለሆነም የአንድ ሰው መብት ብቻ ሳይሆን ከ500 በላይ የሆኑ ተሰብሳቢዎች መብትም መከበር እንዳለበትና ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ግን በአንድ በኩል ስለሰብአዊ መብት መከበር የሚናገሩ ሲሆን በሌላ በኩል ግን እንዴት መብትን እንደሚጋፉ ስለሚታይ ሀሳባቸውን በሥነ ሥርዓት መግለጽ እንዳለባቸው አመልክተዋል ።

ቀጥሎም ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ከክልል 5 የሕገ መንግሥቱ የመጨረሻው ፓራግራፍ " ይህ ሕገ መንግሥት ከዚህ በላይ ለገለጽናቸው ዓላማዎችና ዕምነቶች ማሰሪያ እንዲሆነን እንዲወክሉን መርጠን በላክናቸው ተወካዮቻችን አማካይነት በሕገ መንግሥት ጉባኤ አፅድቀነዋል ። " ስለሚል በቅድሚያ በሕገ መንግሥቱ ይዘቶች መወያየት እንጂ በመግቢያው ከተጀመረ አስቸጋሪ እንደሆነ ጠቁመው በጉዳዩ ላይ በቂ ውይይት ስለተካሄደበት ድምፅ እንዲሰጥበት የውሳኔ ሀሳብ አቅርበዋል ።

በማስከተልም የጉባኤው ሊቀመንበር ጉባኤው ወደ ድምፅ አሰጣጥ እንዲገባ በቀረቡት ሁለት ሀሳቦች ላይ የተቃውሞና የድጋፍ ሀሳብ ጠይቀዋል ።

በዚህም መሠረት አቶ ረሺድ መንግሥቱ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል በጉዳዩ ላይ በቂ ወይይት እንደተካሄ ገልጸው መግቢያ በመጨረሻ ላይ ይታይ የሚለውን ሀሳብ እንደሚቀበሉት ፣ በመድረኩ አመራርም ሆነ በኮሚቴ አማካይነት ለሰነዱ ሌላ መግቢያ ሊዘጋጅ እንደሚገባው አስተያየት ሰንዝረዋል ።

በሌላ በኩል ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ ከክልል 1 መግቢያው የሕገ መንግሥቱን አጠቃላይ ይዘት ስለሚያስቀምጥ ብቁ መሆኑን ወይም አለመሆኑን ምላሽ የሚያገኘው ጠቅላላ የሕገ መንግሥቱን ይዘት ከታየ በኋላ ስለሆነ ሌላ መግቢያ ይዘጋጅ የሚል ሀሳብ አሁን መነሳት እንደሌለበት ጠቁመው የቀረበውን የውሳኔ ሀሳብ መሠረት በማድረግ ድምፅ ወደ መስጠት እንዲገባ አሳስበዋል ።

በተጨማሪም አቶ አለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 መግቢያው አሁን ባለበት ቦታ እንጂ ወደ ኋላ የማይቀየር መሆኑንና ጥያቄው አሁን እንወያይበት ወይስ በይዘቶች ላይ ተወያይተን ከጨረስን በኋላ ይሁን የሚል እንደሆነ ጠቅሰው ሌላ መግቢያ እንዲዘጋጅ የቀረበው ሀሳብ የጉባኤውን ወይይት በተሳሳተ መልክ ከመረዳት እንደሚመስላቸው አመልክተዋል ።



ቀጥሎም የጉባኤው ሊቀመንበር በጉዳዩ ላይ የሚካሄደው ውይይት ይቁም ወይስ ይቀጥል የሚለውን ሀሳብ ለድምፅ አቅርበውት ውይይቱ ይቁም የሚለው ሀሳብ ከ3 ድምፀ ተአቅቦ በስተቀር በተቀሩት የጉባኤው አባላት ተደገፎ ፀድቋል ።

አስከትለውም የሕገ መንግሥቱ መግቢያ ከአሁን ጀምረን እንወያይበት የሚልና በሌሎቹ የሕገ መንግሥቱ ይዘቶች ላይ ከተወያየናና እነሱን ካጠናቀቅን በኋላ በመግቢያው ላይ ተመልሰን እንወያይበት የሚሉ ሁለት ሀሳቦች ለድምፅ አቅርበው የሕገ መንግሥቱን መግቢያ በመጨረሻ ላይ እንወያይበት የሚለው ሀሳብ 514 የድጋፍ ድምፅ ፣ 5 ድምፀ ተአቅቦና ያለምንም ተቃውሞ በማግኘቱ በድምፅ አልፏል ።

ቀጥሎም አቶ አሊ አብዶ ከክልል 14 ጉባኤው ታሪካዊ ሕገ መንግሥቱን ለማፅደቅ በሕዝብ ተመርጦ የተወከለ በመሆኑ ያለውን ጊዜ በዲሞክራሲያዊ አካሄድ በመጠቀም የተጣለበትን ኃላፊነት መወጣት እንዲችል የሚቀርቡትን ሀሳቦች ግንዛቤ ውስጥ ማስገባት ስላለበት የነፍጠኞችን ቅዠትና የተረት አባቶች ተረትን ለማዳመጥ ጊዜ እንደማይኖረው ፣ ስለዚህ በተወካዮች ምክር ቤት ፀድቆ የቀረበውን ሕገ መንግሥት ለጉባኤው መነሻ ይሆናል በሚል ጉባኤው ወስኖ ስለተቀበለውና ሌላ አማራጭ ስላልመጣ ከ30 እስከ 80 ገጽ በጽሑፍ እየቀረበ የጉባኤውን አመራር አካላት ጊዜ ማባከን ተገቢና አስፈላጊ ስለማይሆን መድረኩ ተገቢውን ትኩረት እንዲያደርግ አሳስበዋል ።

በሌላ በኩል አቶ ዘለሌ ፀጋሥላሴ ከክልል 14 በጉባኤው ውስጥ ከ500 በላይ የሕዝብ ተወካዮች ያሉ መሆናቸውንና ምናልባት አብዛኛዎቹ ተመሳሳይ አመለካከት ሊኖራቸው እንደሚችል ጠቅሰው ተቃውሞ ሆነ የተለየ ሀሳብ ያለው ሰው በሚያቀርበው ሀሳብ ተቃውሞ ካለ ሥነ ሥርዓት ባለው መልክ ማቅርብ እንጂ ሞራልን በሚነካ መንገድ መሆን እንደሌለበት ፣ ለምሳሌ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ በሚመስላቸው አመለካከት እርሳቸው በሚገባቸው መልክ ተቃውሞችን እንደሚያቀርቡ ፣ ሥነ ሥርዓት ካልጠበቁና ማቅረብ የሚገባቸውን በተገቢው ቦታ ካላቀረቡ በማሳሰቢያም ሆነ በሌላ መልክ እንዲያስተካክሉ መደረግ እንደሚኖርበት ፣ ከዚህ ውጭ ነፍጠኛ ፣ ትምክህተኛ እየተባለ ሰዎችን እንዳይናገሩ አፍ የማስያዝና የማሸማቀቅ አካሄድ ትክክል እንዳልሆነ ገልጸዋል ።

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር ባደረጉት ገለጻ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ የጉባኤው አመራር አካል ሰብአዊ መብትን አያከብርምና ዲሞክራሲያዊ አይደለም በማለት በግልጽ ሲናገሩ የነበረ ሲሆን አቶ አሊ አብዶ የተናገሩት ግን ቀደም ሲል ተነስቶ

ስለነበረው የሥነ ሥርዓት ማሳሰቢያ እንጂ ስለሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ባለመሆኑ የአቶ
ዘለሌ ፀጋሥላሴ የሥነ ሥርዓት አስተያየት ተቀባይነት እንደሌለው ፣ ሻለቃ አድማሴ
ዘለቀ ግን በጽሑፍ ያስፈሯዋቸው ጉዳዮች ካሉ በጉባኤው ውስጠ ደንብ መሠረት
ለማቅረብ እንደሚችሉ ነገር ግን ጽሑፍ አለኝ ብለው ደጋግመው በጉባኤው ውስጥ
ማንሳት እንደሌለባቸው አስገንዝበዋል ::

ቀጥሎም አንድ የጉባኤ አባል ሕገ መንግሥቱ ሕዝብ ያኮረፈበት ነው ሲባል
ተናጋሪው የሚወክለውን ሕዝብ ለማለት መሆኑን የተለያዩ ታዛቢዎችና የዜና
ማሰራጫ አውታሮች እንዲሁም በትክክል ቋንቋው የማይገባቸው አካላት ሊገነዘቡት
እንደሚገባ አሳስበዋል ::

በመጨረሻም አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 የጉባኤው አመራር
በውይይቱ አካሄድ ማሳሰቢያው ይጠቅማል ካለ ሊቀበል ፣ አይጠቅምም ካለ ደግሞ
ብዙ እጅም ቢወጣ ላይቀበል እንደሚችል ጠቁመው በማሳሰቢያ ምክንያት ጊዜን
ላለማጥፋትና ውይይቱን ላለማጓተት መድረኩ ወደ ቀጣዩ ሂደት እንዲያመራ
አሳስበው ጉባኤው ከሟቱ 4:45 ለሻይ ዕረፍ ተነስቷል ::

ከሻይ ዕረፍት በኋላ ጉባኤው ውይይቱን የቀጠለው በሕገ መንግሥት ኮሚሽን
ተዘጋጅቶ በተወካዮች ምክር ቤት በታየውና ጉባኤው ጥቅምት 19 ቀን 1987 ዓ.ም
በተረከበው የሕገ መንግሥት ረቂቅ ላይ ነው ::

በመጀመሪያም የጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሳ ጊዳዳ ጉባኤው ቀደም ሲል
በወሰነው መሠረት ውይይቱ በምዕራፍ አንድ በጠቅላላ ድንጋጌዎች ከሚለው ጀምሮ
አንቀጽ በአንቀጽ እንደሚቀጥል ገልጸው በአንቀጽ 1 የኢትዮጵያ መንግሥት ስያሜ
በሚለው ላይ አስተያየት ማቅረብ እንደሚቻል ገልጸዋል ::

በዚሁም መሠረት አቶ አብዱራህማን መሐመድ ከክልል 6 በሰጡት አስተያየት
የኢትዮጵያ መንግሥት ስያሜ ሲነሳ በቅድሚያ በኢትዮጵያ የነበሩት አገዛዞች ማየት
እንደሚያስፈልግ ፣ ንጉሣዊው የዘውድ አገዛዝ የጥቂቶች አምባገነንነት የሰፈነበት ፣
በአንፃሩም የሕዝብ የበላይነት ያልነበረበት እንደሆነ ጠቁመው የብሔር ብሔረሰቦች
መብትና ሕልውና የተረገጠበት እንደነበር አመልክተዋል ::

አያይዘውም ከንጉሣዊ አገዛዝ የአምባገነኑ የደርግ መንግሥት አገዛዝ የሰው
ሕይወት ርካሽ የነበረበት እና ብሔር ብሔረሰቦች ከራሳቸው አካባቢ ወይም
ከንብረታቸው እንዲፈናቀሉ የተደረገበት እንደነበር አውስተው ሕዝቡ ከፍተኛ ትግል
ያደረገውና ዛሬም አዲስ ሕገ መንግሥት ያስፈለገው ከዚህ ዓይነቱ ጭቆና ለመላቀቅ
መሆኑ በአሁኑ ጊዜ በኢትዮጵያ መቀረጽ ያለበት ሕገ መንግሥት የብሔር



ብሔረሰቦችን እኩልነት የሚረጋገጥበት ፣ መብታቸው የሚከበርበት ፣ ለአንድ ሙቶ
ዓመት ያህል የተነጠቁትን የፖለቲካ ሥልጣን እንዲያገኙ ሁኔታዎችን የሚያመቻችና
ዲሞክራሲያዊ መሆን እንዳለበት ገልጸዋል ::

አስከትለውም ድርጅታቸው የቤንሻንጉል ሕዝብ ነፃነት ንቅናቄ / ቤሕነን / እና
የቤንሻንጉል ሕዝብ ኢትዮጵያን ከመበታተን የሚያድናት መሠረታዊና ቁልፍ ጉዳይ
ፌዴራላዊ የመንግሥት አደረጃጀት እንደሆነ የሚያምን በመሆኑ ስያሜው በረቂቁ
በተቀመጠው መልኩ ፌዴራላዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፐብሊክ በሚለው መቀመጡ
እንደሚደግፉ አመልክተዋል ::

ቀጥሎም አቶ ዚያድ ዳውድ ከክልል 5 ጉባኤው የኢትዮጵያ ሕዝቦች በራሳቸው
የመብት ጥያቄ ላይ የሚነጋገሩበት በመሆኑ ታሪካዊ እንደሆነ ፣ ከዚህ ቀደም
የነበሩት ሥርዓቶች የአንድ ወገን የኢኮኖሚ መዋቅር ፣ ባህልና የአኗኗር ሥርዓት
በሌሎች ላይ የሚያሰርፁ እንደነበሩ ፣ ይህንንም ለማስወገድ ሕዝቦች መሣሪያ
እንዲያነሱ መገደዳቸውንና ለዚህ ዲሞክራሲያዊ መድረክ መደረሱን አስረድተው
የኢትዮጵያ ሕዝቦችና ብሔር/ብሔረሰቦች ከዚህ ቀደም የነበረውን ብሶትና ሰቆቃ
የሚያስወግድ ፣ ተከባብረውና ተፈቃቅረው ለመኖር የሚያስችል መንገድ እንዲቀየስ
በአጠቃላይ አዲስ የመንግሥት ሥርዓት ጉባኤው እንዲቀርጽ የሚጠበቅ መሆኑን
ገልጸዋል ::

አያይዘውም የመንግሥት ስያሜን በተመለከተ የኢትዮጵያ ብሔር ብሔሰቦች
እንዳልኮሩበት ፣ አሁን ለአዲስቷ ኢትዮጵያ አዲስ ስም ማውጣት እንደሚያስፈልግና
በረቂቁ ላይ የተቀመጠው ስያሜም ፌዴራላዊነትና ዲሞክራሲያዊነትን ያካተተ
በመሆኑ እንደሚደግፉት ፣ በአጠቃላይ የኢትዮጵያ ብሔር ብሔረሰቦች
በዲሞክራሲያዊ ሥርዓት ተፈቃቅደው የሚኖሩበት ፈቃዳቸውም ሆኖ የሚለያዩበት
ሁኔታ ከወዲሁ ግልጽ መሆን እንዳለበት አመልክተዋል ::

አቶ አለማየሁ አለሙ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል በሰነዱ ላይ የተቀመ
ጠውን ስያሜ በመደገፍ በሰጡት አስተያየት የኢትዮጵያ መንግሥት ስያሜ ምን
ይሁን የሚለውን ለመመለስ ከዚህ በፊት የነበሩ መንግሥታት አዋቃቀሮች ለሕዝቡ
ያስገኙት ጥቅም ምንድነው ? የሚለውን መመልከት ተገቢ እንደሆነ ገልጸው
አወቃቀሩ አሃዳዊ ሆኖ ሕግ የማውጣት ሆነ የመተርጎም ሥልጣን በሞኖፖል ተይዞ
አመራር ከላይ ወደታች እየወረደ ሕዝቦችን በአምባገነንነት ለመግዛት የሚያስችል
እንደነበረ አስረድተዋል ::

ስለነበረው የሥነ ሥርዓት ማሳሰቢያ እንጂ ስለሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ባለመሆኑ የአቶ ዘለሌ ፀጋሥላሴ የሥነ ሥርዓት አስተያየት ተቀባይነት እንደሌለው ፣ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ግን በጽሑፍ ያስፈሯቸው ጉዳዮች ካሉ በጉባኤው ውስጠ ደንብ መሠረት ለማቅረብ እንደሚችሉ ነገር ግን ጽሑፍ አለኝ ብለው ደጋግመው በጉባኤው ውስጥ ማንሳት እንደሌለባቸው አስገንዝበዋል ::

ቀጥሎም አንድ የጉባኤ አባል ሕገ መንግሥቱ ሕዝብ ያኮረፈበት ነው ሲባል ተናጋሪው የሚወክለውን ሕዝብ ለማለት መሆኑን የተለያዩ ታዛቢዎችና የዜና ማሰራጫ አውታሮች እንዲሁም በትክክል ቋንቋው የማይገባቸው አካላት ሊገነዘቡት እንደሚገባ አሳስበዋል ::

በመጨረሻም አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 የጉባኤው አመራር በውይይቱ አካሄድ ማሳሰቢያው ይጠቅማል ካለ ሊቀበል ፣ አይጠቅምም ካለ ደግሞ ብዙ እጅም ቢወጣ ላይቀበል እንደሚችል ጠቀመው በማሳሰቢያ ምክንያት ጊዜን ላለማጥፋትና ውይይቱን ላለማጓተት መድረኩ ወደ ቀጣዩ ሂደት እንዲያመራ አሳስበው ጉባኤው ከሟቱ 4:45 ለሻይ ዕረፍ ተነስቷል ::

ከሻይ ዕረፍት በኋላ ጉባኤው ውይይቱን የቀጠለው በሕገ መንግሥት ኮሚሽን ተዘጋጅቶ በተወካዮች ምክር ቤት በታየውና ጉባኤው ጥቅምት 19 ቀን 1987 ዓ.ም በተረከበው የሕገ መንግሥት ረቂቅ ላይ ነው ::

በመጀመሪያም የጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሳ ጊዳዳ ጉባኤው ቀደም ሲል በወሰነው መሠረት ውይይቱ በምዕራፍ አንድ በጠቅላላ ድንጋጌዎች ከሚለው ጀምሮ አንቀጽ በአንቀጽ እንደሚቀጥል ገልጸው በአንቀጽ 1 የኢትዮጵያ መንግሥት ስያሜ በሚለው ላይ አስተያየት ማቅረብ እንደሚቻል ገልጸዋል ::

በዚህም መሠረት አቶ አብዱራሀማን መሐመድ ከክልል 6 በሰጡት አስተያየት የኢትዮጵያ መንግሥት ስያሜ ሲነሳ በቅድሚያ በኢትዮጵያ የነበሩት አገዛዞች ማየት እንደሚያስፈልግ ፣ ንጉሣዊው የዘውድ አገዛዝ የጥቂቶች አምባገነንነት የሰፈነበት ፣ በአንፃሩም የሕዝብ የበላይነት ያልነበረበት እንደሆነ ጠቁመው የብሔር ብሔረሰቦች መብትና ሕልውና የተረገጠበት እንደነበር አመልክተዋል ::

አያይዘውም ከንጉሣዊ አገዛዝ የአምባገነኑ የደርግ መንግሥት አገዛዝ የሰው ሕይወት ርካሽ የነበረበት እና ብሔር ብሔረሰቦች ከራሳቸው አካባቢ ወይም ከንብረታቸው እንዲፈናቀሉ የተደረገበት እንደነበር አውስተው ሕዝቡ ከፍተኛ ትግል ያደረገውና ዛሬም አዲስ ሕገ መንግሥት ያስፈለገው ከዚህ ዓይነቱ ጭቆና ለመላቀቅ መሆኑ በአሁኑ ጊዜ በኢትዮጵያ መቀረጽ ያለበት ሕገ መንግሥት የብሔር



ብሔረሰቦችን እኩልነት የሚረጋገጥበት ፣ መብታቸው የሚከበርበት ፣ ለአንድ መቶ ዓመት ያህል የተነጠቁትን የፖለቲካ ሥልጣን እንዲያገኙ ሁኔታዎችን የሚያመቻችና ዲሞክራሲያዊ መሆን እንዳለበት ገልጸዋል ::

አስከትለውም ድርጅታቸው የቤንሻንጉል ሕዝብ ነፃነት ንቅናቄ / ቤሕነን / እና የቤንሻንጉል ሕዝብ ኢትዮጵያን ከመበታተን የሚያድናት መሠረታዊና ቁልፍ ጉዳይ ፌዴራላዊ የመንግሥት አደረጃጀት እንደሆነ የሚያምን በመሆኑ ስያሜው በረቂቁ በተቀመጠው መልኩ ፌዴራላዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፐብሊክ በሚለው መቀመጡ እንደሚደግፉ አመልክተዋል ::

ቀጥሎም አቶ ዚያድ ዳውድ ከክልል 5 ጉባኤው የኢትዮጵያ ሕዝቦች በራሳቸው የመብት ጥያቄ ላይ የሚነጋገሩበት በመሆኑ ታሪካዊ እንደሆነ ፣ ከዚህ ቀደም የነበሩት ሥርዓቶች የአንድ ወገን የኢኮኖሚ መቆጣጠር ፣ ባህልና የአኗኗር ሥርዓት በሌሎች ላይ የሚያሰርፁ እንደነበሩ ፣ ይህንንም ለማስወገድ ሕዝቦች መሣሪያ እንዲያነሱ መገደዳቸውንና ለዚህ ዲሞክራሲያዊ መድረክ መደረሱን አስረድተው የኢትዮጵያ ሕዝቦችና ብሔር/ብሔረሰቦች ከዚህ ቀደም የነበረውን ብሶትና ሰቆቃ የሚያስወግድ ፣ ተከባብረውና ተፈቃቅረው ለመኖር የሚያስችል መንገድ እንዲቀየስ በአጠቃላይ አዲስ የመንግሥት ሥርዓት ጉባኤው እንዲቀርጽ የሚጠበቅ መሆኑን ገልጸዋል ::

አያይዘውም የመንግሥት ስያሜን በተመለከተ የኢትዮጵያ ብሔር ብሔሰቦች እንዳልኮሩበት ፣ አሁን ለአዲስቷ ኢትዮጵያ አዲስ ስም ማውጣት እንደሚያስፈልግና በረቂቁ ላይ የተቀመጠው ስያሜም ፌዴራላዊነትና ዲሞክራሲያዊነትን ያካተተ በመሆኑ እንደሚደግፉት ፣ በአጠቃላይ የኢትዮጵያ ብሔር ብሔረሰቦች በዲሞክራሲያዊ ሥርዓት ተፈቃቅደው የሚኖሩበት ፈቃዳቸውም ሆኖ የሚለያዩበት ሁኔታ ከወዲሁ ግልጽ መሆን እንዳለበት አመልክተዋል ::

አቶ አለማየሁ አለሙ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል በሰነዱ ላይ የተቀመ ጠውን ስያሜ በመደገፍ በሰጡት አስተያየት የኢትዮጵያ መንግሥት ስያሜ ምን ይሁን የሚለውን ለመመለስ ከዚህ በፊት የነበሩ መንግሥታት አዋቃቀሮች ለሕዝቡ ያስገኙት ጥቅም ምንድነው ? የሚለውን መመልከት ተገቢ እንደሆነ ገልጸው አወቃቀሩ አሃዳዊ ሆኖ ሕግ የማውጣት ሆነ የመተርጎም ሥልጣን በሞኖፖል ተይዞ አመራር ከላይ ወደታች እየወረደ ሕዝቦችን በአምባገነንነት ለመግዛት የሚያስችል እንደነበረ አስረድተዋል ::

ከሽግግር መድረኩ ወዲህ እየታየ ያለው ሁለተኛው አማራጭ መሆኑንና ይህም የጠነከረ አንድነት በሕዝቦች ፍቅር ፣ መተማመንና እኩልነት አንድነት ሊመጣ ይችላል የሚለው ሲሆን ሀገሪትን የብሔ ብሔር/ብሔረሰቦችና ሕዝቦች ሀገር በመሆኗ እያንዳንዱ በሽግግር መድረኩ በተመቻቸለት ሁኔታ የራሱን አካባቢያዊና ክልላዊ ጉዳዮችን ራሱ ከየና በፌዴራላዊ ትስስር ክልሎች ወደ ጠንከረ አንድነት እንደሚመጡ ጠቅሰው ፌዴራላዊ ትስስር ክልሎች በጋራ የሚያገናኟቸውን ጉዳዮች በማዕከል የሚፈቱበት ፣ የራሳቸውን ጉዳይ ራሳቸው የሚያዩበትና የሚፈቱበት ሥርዓት እንደሆነ አብራርተዋል ::

አያይዘውም የጠነከረ አንድነት ሊመጣ የሚችለው ልዩነቶችን አምኖ በመቀበል በልዩነቶች ውስጥ የጠነከረ አንድነት ለማምጣት እንቅስቃሴ ሲደረግ መሆኑን ገልጸው ይህም ሕዝቦች ሲጋራ ጥቅሞቻቸው ተባብረው እንዲኖሩ የሚያደርጋቸው በብሔራዊ ማንነት ልዩነት ላይ የሚሞረኮዝ አንድነት እንደሆነ ፣ ፌዴራሊዝም የሕዝቦች ቋንቋ እንዲያድግ ፣ ታሪካቸው እንዲከበር ፣ በአካባቢያዊ ጉዳዮች ላይ ለመወሰን የሚያስችላቸውን ማንነታቸውን ለማረጋገጥ የሚያደርጉት ትግል የሚያጎለብትና የጠነከረ አንድነትንም የሚያመጣ መሆኑን አስረድተዋል ::

እነዚህ ነገሮች ሊከበሩ የሚችሉት በፌዴራላዊ ትስስር ሕዝቦች በመፈቃቀድ ፣ በነፃ እምነታቸውና ፍላጎታቸው ይበጀናል ብለው የሚቀበሉት መድረክ ሲመቻች መሆኑና ያለውም መድረክ ይህን የሚያመቻች እንደሚመስላቸው ገልጸዋል ::

በመጨረሻም ፌዴራሊዝም ያለ ሙሉ ዲሞክራሲ ተግባራዊ ሊሆን እንደማይችል ፣ ዲሞክራሲያዊነትም የሕዝብን ሉዓላዊነት መሠረት ያደረገ በራሱም ሆነ በጋራ ጉዳዮች ላይ ያልተገደበ ፍላጎቱን ሊገልጽበት የሚችልበትን ሁኔታ የሚያመቻችና የራስን ዕድል ለመወሰን የሚያስችል መብት እንደሆነ ፣ የሚመሠረተውም ፌዴራላዊ ብቻ ሳይሆን ዲሞክራሲያዊውም መሆን ስላለበት በአንቀጹ የተቀመጠው ስያሜ ተገቢ እንደሆነ አመልክተዋል ::

አቶ እስራኤል ቶጋ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል የኢትዮጵያ ስያሜ ምን ይሁን በሚለው ላይ ሲመክሩ በወላይታነታቸው ኩራት እንደሚሰማቸውና ይህንን በተመለከተም በሰጡት አስተያየት አዲሱ አወቃቀር ቀደም ሲል የነበረውን ልዩነት የሚያስወግድ ልዩነቱ የፈጠረውን ጦርነትና ስደት የሚገታ ኢትዮጵያም እንደ እናት ልጆቿን ሰብስባ መያዝ የሚያስችላት እና በአጠቃላይ የብሔር /ብሔረሰቦች መብት የሚከበርበት ፣ ባህልና ቋንቋቸው የሚዳብርበት እንደሆነ ጠቅሰው ሕገ መንግሥቱ ብሔር /ብሔረሰቦች የራሳቸውን ዕድል በራሳቸው ለመወሰን የሚያችል መሆን እንዳለበትና ከዚህ አንፃርም የአዲሲቷ ኢትዮጵያ ስያሜ በረቂቁ ላይ



እስከትለውም ይህንኑ በመቃወም ሕዝቦች ለዘመናት ታግለው ለባሬው ምዕራፍ መድረሳቸውን ጠቅሰው ጉባኤው መነጋገር ያለበትም የኢትዮጵያ ብሔር/ብሔረሰቦች የራሳቸውን ዕድል በራሳቸው እንዴት መወሰን እንደሚችሉና አዲሲቷን ኢትዮጵያ እንዴት በመፈቃቀር ሊገነቡ ይችላሉ በሚለው ላይ መሆን እንዳለበት ፣ ከዚህ አንፃር እንደ ኢትዮጵያ ያለች ብዙ ብሔር/ብሔረሰቦች ለሚኖሩባት አገር ተስማሚው የመንግሥት አወቃቀር ፌዴራላዊ መሆኑን ጠቅሰው ፌዴራሊዝም ብሔር/ ብሔረሰቦች የራሳቸውን ዕድል በራሳቸው እንዲወስኑ ፣ የአካባቢያቸውን ጉዳይ በአካባቢያቸው እንዲያዩ ፣ ባህላቸውን እንዲያሳድጉ ፣ መብታቸውን እንዲያስከብሩና በአጠቃላይ ተፈቃቅረው በአንድነት እንዲኖሩ የሚያስችል የመንግሥት አወቃቀር እንዲሆንና ዲሞክራሲ የሚረጋገጠው በፌዴራሊዝም እንደሆነ ዲሞክራሲ ያለ ፌዴራሊዝም ዕውን ሊሆን እንደማይችልና አወቃቀሩም ሕዝቦች በማዕከላዊ መንግሥት ተገቢ ውክልና እንዲኖራቸው ሊያደርግ እንደሚችል እንዲሁም የኢትዮጵያ መንግሥት ስያሜ የሚረቀቀውን ሕገ መንግሥት ይዘት የሚያንፀባርቅ መሆን እንዳለበትና በረቂቁ የተቀመጠው የመንግሥት ስያሜ ፌዴራላዊና ዲሞክራሲያዊ በመሆኑ እንደሚደግፉት አብራርተዋል ::

አቶ አብዱልራህት መሐመድ ከክልል 14 የሚበጀው የመንግሥትን ሥርዓት ለመምረጥ የአገሪቱን ያለፈ ታሪክ መቃኘት አግባብ እንደሆነ በሰጡት አስተያየት በኢትዮጵያ የፖለቲካ መድረክ የአንድነትና የብሔራዊ መብት ጥያቄ ቁልፍና አንገብጋቢ ሆኖ ለዘመናት መቆየቱን ፣ ይህም በአገሪቱ ለተካሄዱት ጦርነቶችና ግጭቶች ብቸኛ መንስኤ እንደሆነ ፣ ስሬ የብሔር ብሔረሰብ ተዋጽኦና ውክልና ያለው ይህ ጉባኤ በመጀመሪያ ደረጃ መንደርደሪያ አድርጎ ቀደም ሲል የነበሩትን እንቅፋቶች ሊወገዱ የሚችሉባቸውን ሁኔታዎች ማየት እንዳለበት አሳስበዋል ::

አይይዘውም የጠነከር አንድነት በመፈለግ ገገርዎችና አፈንጉዎች ሳያካሂዱት የቆዩት ጦርነትና የግዛት አንድነት አመለካከት እንደነበረ ግን እንዳላዋጣ ፣ በኋላም ከየካቲት 1966 ዓ.ም በፊት የኢትዮጵያ ተማሪዎች እንቅስቃሴ ከፍተኛ ደረጃ ላይ እንደደረሰ ተማሪዎች ቀስ በቀስ በተለይዩ የፖለቲካ ኃይሎች በተለያየ መልክና ደረጃ ሲገፉበት ቆይተው በሽግግሩ ቻርተር የሰፈረው ዲሞክራሲያዊ የሕዝቦች አንድነት እንዲመጣ በመርህ ደረጃ እንደተቀመጠ ፣ አሁንም የጠነከረ አንድነት እንዴት ይመጣል የሚለውን ማየት እንደሚያስፈልግ አስረድተዋል ::

ቀጥለውም በአማራጭ አንድ ፣ አንድነት በኃይል ፣ በዐምብ በግረስ እና ሕዝብ ላይ ጫና በማሳደር ሊመጣ እንደማይችል ከራሳችን ታሪክ መማር እንደሚቻል ገልጸዋል ::

እንደተቀመጠው ፌዴራላዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፐብሊክ መባሉን እንደሚደግፉ አመልክተዋል ።

አቶ ሁሴን መሐመድ ከክልል 4 በበኩላቸው ትናንት የኢትዮጵያ ሕዝብ ለስውር ባርነት ተዳርጎ የቆየበት ወቅት እንደነበር አስታውሰው ይህ እንዳይደገም አዲስ ስልት መቀየስ አስፈላጊ መሆኑን ገልጸው ዛሬ ኢትዮጵያዊነት ሳይፈልጉት የሚጫን ሳይሆን የእያንዳንዱ ኢትዮጵያዊ መለያና ክብር እንደሆነ ጠቅሰዋል ።

አስከትለውም የመንግሥት አወቃቀር በኢትዮጵያ ፌዴራላዊ መሆን እንዳለበትና ይህም ብሔር/ብሔረሰቦች በራሳቸው እንዲተማመኑ ብቻ ሳይሆን በመንፈሳዊ ቅናት በመነሳሳት ለልማትና በአጠቃላይ ለማህበራዊ ዕድገት ልዩ መሠረት የሚጥል እንደሆነ ፣ ሥርዓቱ ለአንድነትና ለባህል ዕድገት ምቹ ሁኔታን እንደሚፈጥርም እንደ ሲዊዘርላንድ ፣ ጀርመንና ጣሊያን ካሉ የአውሮፓ አገሮች መማር እንደሚቻል ጠቁመው በአጠቃላይ ስያሜው ይበልጥ የሚያፈቅቅርና ለአንድነት የሚያነሳሳ ፣ ለመበታተን ተቃርባ የነበረችውን አገር የሚያድን በመሆኑ በረቂቁ ላይ የተቀመጠው ስያሜ እንደሚደግፉት አስረድተዋል ።

አቶ አወጣ ገብሩ ከክልል 3 ስያሜውን በመደገፍ በሰጡት አስተያየት ባሳለፍናቸው ሥርዓቶች ሥልጣን በሞኖፖሊ ተይዞ ብሔራዊና መደባዊ ጭቆናዎች በሰፊው ሕዝብ ላይ ሲፈራረቁበት እንደነበር ፣ ስያሜው ይህንን ብቻ የሚያስወግድ ሳይሆን ተግባራዊ ሊሆን የሚችል እንደሆነ ጠቅሰው ሕዝቡ በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ላይ ውይይት ሲደረግ እሳቸው በተመረጡበት አካባቢ ያለው ሕዝብ በረቂቁ የተቀመጠውን ስያሜ መደገፉንና ይህንኑ ስያሜ እንዲያፀድቁት መላካቸውን አመልክተዋል ።

በሌላ በኩል አቶ ዳንኤል በላይነህ ከክልል 14 በመርሀ ደረጃ ፌዴራላዊ አወቃቀርን በመደገፍ በአንቀጹ የተቀመጠውን ስያሜ እንደሚቀበሉት ገልጸው አወቃቀሩ ግን በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ አንቀጽ 47 እንደተቀመጠው የትግራይ ፣ የአፋር ፣ የአማራ ፣ የኦሮሞ ፣ የሶማሌ ፣ የቤንሻንጉል ፣ የደቡብ ሕዝቦች ፣ የጋምቤላ ፣ የሐረሪ በሚል በጎሳ ላይ የተመሠረተ መሆን እንደሌለበት ፣ በጎሳ ላይ የተመሠረተ ፌዴራላዊ አወቃቀር ወንድማማችነትን የሚያራርቅ ፣ ሕዝቡን የሚበታትንና አብሮ የመኖር ተስፋን የሚያጨልም ፣ በአጠቃላይ አንዲት ኢትዮጵያን አንድ አድርጎ ከመገንባት ይልቅ ለመበታተን ከፍተኛ አስተዋጽኦ የሚያደርግ እንደሆነ ገልጸዋል ።

አያይዘውም በእሳቸው እና በክልል 14 ወረዳ 16 ሕዝብ እምነት የፌዴራሉ አባል ክልሎች በአፄ ኃይለ ሥላሴ የነበሩት 14 ጠቅላይ ግዛቶች ለምሳሌ ጎጃም ፣





ወለጋ ወዘተ… እንጂ በረቂቁ የተቀመጡት ዘጠኙ መሆን እንደሌለባቸው አውስተዋል ።

በሌላ በኩል አቶ ታሪኩ ፅጌ ከክልል 14 በበኩላቸው ስያሜው ተቃዋሚ ፓርቲዎችን የሚጋብዝ በመሆኑ እንደሚቀበሉት አስታውቀዋል ።

አንድ የክልል 5 ተወካይ በሰጡት አስተያየት አንቀጹን በመደገፍ የተገለጹትን ሀሳቦች እንደሚቀበሉ ፣ ከስያሜው ውስጥ " ዲሞክራሲያዊ " የሚለውን ቃል ግን ዲሞክራሲን የማያራምዱ አምባገነን መንግሥታት ለማስመሰል የሚጠቀሙበት በመሆኑ እንደሚያንገሸግሻቸው ገልጸው ዲሞክራሲያዊነትን መጎናፀፍ የሚቻለው በስያሜ ሳይሆን በተግባር በመሆኑ ቃሉ በራሱ ያለመተማመንን ከማመልከቱ ባሻገር የሚሰጠው ፋይዳ ስለሌለው ቢወጣ እንደሚመርጡ አስረድተዋል ።

ይህን ሀሳብ በመደገፍ አቶ መኩሪያ ታፈሰ ከክልል 14 በሰጡት አስተያየት " ዲሞክራሲያዊ " የሚለው ቃል የሚቀንሰው ወይም የሚጨምረው ነገር ባለመኖሩ ቢወጣ የተሻለ እንደሚሆን አመልክተዋል ።

በሌላ በኩል ደግሞ አቶ ዘለሌ ፀጋሥላሴ ከክልል 14 በሰጡት አስተያየት ስያሜው ፌዴራላዊ የመንግሥት ሥርዓትን የሚደነግግ በመሆኑ ሙሉ በሙሉ እንደሚቃወሙት ፣ ኢትዮጵያ አኩሪ ታሪክ ያላት ፣ በአንድነቷ ታፍራና ተከብራ የኖረች ግን ሚዛናዊ መሪና ትሁት አስተዳደር ያላገኘች መሆኗን አስታውቀዋል ።

አያይዘውም በተለያዩ አጋጣሚዎች በጡንቻ ሥልጣን የያዙ መሪዎች ኢትዮጵያውያንን በእኩል ዓይን አለማየታቸውን ፣ ሲጨፈጭፉና ሲያርዱ የኖሩ አምባገነኖች እንደነበሩና ውስጣዊ ሉዓላዊነትን ተፃርረው ከፍተኛ በደል መፈጸማቸውን ፣ መሪዎች ቢፈራረቁም ሕዝቦች ሳይነጣጠሉ አገሪቱ አንድ ሆና መቆየቷን አመልክተው ከዚህ አንፃር የነበረውን ጭቆና የሚያስቀረው ፌዴራላዊ የመንግሥት አወቃቀር ነው የሚለውን እንደማይቀበሉትና ዲሞክራሲያዊ መንግሥት አወቃቀሩ አሃዳዊ ወይም ፌዴራላዊ ሊሆን ስለሚችል ሁለቱንም ያጣጣመ ዲሞክራሲያዊ ማዕከላዊነትን የጠበቀ አደረጃጀት ወይም አወቃቀር መደንገግ እንዳለበት ፣ ስያሜውም የኢትዮጵያ ማዕከላዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፐብሊክ በሚል እንዲቀመጥ ሀሳብ አቅርበዋል ።

አቶ ግርማ ብሩ ከክልል 4 ቀደም ሲል የተነሱትን ነጥቦች በተመለከተ በሰጡት አስተያየት ፌዴራሊዝም እንደተባለው አንድነትን የሚንድ ባለመሆኑ ጉባኤው ቢቀበለውም የተሻለ እንደሚሆንና ፌዴራላዊ አደረጃጀት ካለ ደግሞ ዲሞክራሲያዊ

የሚለው ቃል የፅንስ ሐሳብ እገዛ የሚያደርግ መሆን ስላለበት ዲሞክራሲያዊ የሚለው ቃል የፅንስ ሐሳብ እገዛ የሚያደርግ በመሆኑ ቢቀመጥ የሚጨምር ቢወጣ ግን የሚያጎድል እንደሆነ አብራርተው ዲሞክራሲያዊ የሚለው ቃል ይቀመጥ ማለት ግን ከዚህ ቀደም አምባገነኖች እንደተጠቀሙበት ለሽፋን ብሎም ለጥፋት እንገለገልበት ማለት እንዳልሆነ ገልጸዋል ::

አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 በበኩላቸው በሰጡት አስተያየት በአንድ አገር የተሟላ ዲሞክራሲያዊ ሥርዓት ሳይኖር የተሟላ ፌዴራላዊ አስተዳደር ስለማይጠበቅ "ዲሞክራሲያዊ "እና "ፌዴራላዊ" የሚሉት ቃላት የተሳሰሩበት ሁኔታ መኖሩን በአንፃሩ ደግሞ "ፌዴራላዊ "የሚለው ቃል የሥልጣን ክፍፍል በማዕከልና በክልል በመሆኑን ፣ ዲሞክራሲ የሚለው ደግሞ በሕዝብ ላይ መመሥረትን የሚገልጽ በመሆኑ ቃላቱ የተለያዩ ፅንሰ ሐሳቦችን የሚገልጹና አንዱ አንዱን ሊተካ እንደማይችል አብራርተዋል ::

በተጨማሪም በሀገራችን ያለ ፌዴራላዊ አስተዳደር የሕዝቡን መብት መጠበቅ እንደማይቻል ፣ አወቃቀሩ ማዕከላዊ ይሁን ከተባለ ግን የኢትዮጵያ ሕዝቦች ተመክሮ እንዳላቸውና በሕግ ሥልጣንን የመከፋፈል ልምድ ጋር መኖሩ ብሔር ብሔረሰቦች የሚገባንን ሥልጣን ካልተሰጠን እናምንም ሊሉ እንደሚችሉ ፣ በአጠቃላይ ሁሉም ነገር በመንግሥት ፈቃድ ይሁን እንደማለት ነው ብለዋል ::

አያይዘውም ቀደም ሲል እንደተባለው ፀረ ዲሞክራሲ ኃይሎች በራስ አለመተማመን ዲሞክራሲያዊ የሚለውን ቃል ሲጠቀሙበት መቆየታቸውን ነገር ግን እነርሱ የተጠቀሙበት ሁሉ እርኩስ ነው ከተባለ እነርሱ ያልተጠቀሙበት ቃል ሊታጣ እንደሚችል ጠቆመው ቤቱ በጉዳዩ ላይ ሰፊ ውይይት ማካሄዱን ግምት ውስጥ አስገብቶ እንዲወስን ጠይቀዋል ::

አቶ መኩሪያ ታፈሰ ከክልል 14 በሰጡት አስተያየት ፌዴራል የሚለው ቃል ዲሞክራሲ የሚለውን እንደማያጠቃልል በአንፃሩ ግን ሪፐብሊክ የሚለው ዲሞክራሲን እንደሚያካትት ፣ ዲሞክራሲ የሚለውን ቃል መጠቀሙ አላስፈላጊና ወደ ጥንቱ አስተሳሰብ ይወስዳል የሚል ተቃውሞ አቅርበዋል ::

በመጨረሻም የጉባኤውሊቀመንበር በጉዳዩ ላይ በቂ ውይይት መደረጉንና ከቤቱም ወደ ውሳኔ እናምራ የሚል ሀሳብ መቅረቡን ገልጸው በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ አንቀጽ 1 ላይ " ዲሞክራሲያዊ " እና " ፌዴራላዊ " የሚሉትን ቃላት ይውጡ ወይም አይውጡ በሚሉት ላይ ተራ በተራ ድምፅ እንዲሰጥባቸው ጠይቀዋል ::



በዚህ መሠረትም " ፌዴራላዊ " የሚለው ቃል እንዳለ ይሁን የሚለውን በመደረፍ 524 ፣ በመቃወም 1 ፣ ድምፀ ተአቅቦ 2 ተመዝግቦ ቃሉ እንዳለ እንዲሆን ሲወሰን " ዲሞክራሲያዊ " የሚለው ቃል እንዳለ ይሁን የሚለውን በመደረፍ 524 ፣ በመቃወም 2 ፣ ድምፀ ተአቅቦ 1 ተመዝግቦ ቃሉ እንዳለ እንዲቀመጥ ተወስኗል ::

ከዚያም አንቀጹ እንዳለ መፅደቁን ለማረጋገጥ በተሰጠው ድምፅ ድጋፍ 526 ድምፀ ተአቅቦ 4 ተመዝግቦ ያለምንም ተቃውሞ አንቀጽ ፀድቆ የዕለቱ ስብሰባ ከቀኑ 7:15 አብቅቷል ::

ጥቅምት 29 ቀን 1987 ዓ.ም ከጧቱ 3:00 በሕገ መንግሥት ጉባኤ አዳራሽ የተካሄው ቀጣይ የሕገ መንግሥት ጉባኤ ስብሰባ የተመራው በጉባኤው ሊመንበር በዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ሲሆን በቅድሚያ የዕለቱ አጀንዳ በረቂቅ የሕገ መንግሥት አንቀጽ 2 የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን በሚለው ላይ ውይይት እንደሚካሄድ አውስተው በአንቀጹ ላይ አስተያየት ካለ ለቀርብ እንደሚችል ማቅረብ እንደሚቻል ገልጸዋል ::

በዚህም መሠረት አቶ ረምረም ሀብታሙ ከክልል 3 አንቀጽ 3 እንደ ከዚህ ቀደሙ ኢትዮጵያዊ ማለት ሌሎች ኢትዮጵያዊ ነው ብለው የሚወስኑት ሳይሆን ራሱ ሕዝቡ ኢትዮጵያዊ ነኝ ብሎ የሚወስንበትና ኢትዮጵያ ማለትም በፌዴሬሽን አባልነት የሚጠቃለሉት ብሔር / ብሔረሰቦችና ሕዝቦች አብረው ለመኖር እስከ ፈቀዱ ድረስ የሚኖሩበትን አካባቢ የሚያጠቃልል መሆኑን የሚያመለክት እንደሆነ በተጨማሪም አንቀጹ ኢትዮጵያ የፈረማቻቸውን ዓለም አቀፍ ስምምነቶችን የሚያከብር በመሆኑ ከጎረቤት አገሮች ጋር መልካም ጉርብትናንና ዝምድናን የሚያጠናክር በመሆኑ የአንቀጹ አቀራረጽ በተቀመጠው መልክ ትክክለኛ እንደሆነ ገልጸዋል ::

ቀጥሎም ወ/ሮ ራሀመት የሱፍ ከክልል 3 በሰጡት አስተያየት ከዚህ ቀደም ኢትዮጵያውያን ለአስከፊ እርስ በርስ እልቂትና ደም መፋሰስ የዳረጉት የኢትዮጵያ ዳር ድንበር ሕዝቦቿ በነፃ ፈቃዳቸው ሳይሆን ሌሎች ከዚህ እስከዚያ ብለው በመወሰናቸው መሆኑን ፣ አንቀጽ 2 ግን ሕዝቦች በነፃ በፈቃዳቸው አብረው ለመኖርና ራሳቸውን በራሳቸው ለማስተዳደር ያላቸውን መብት የሚያረጋግጥ ፣ የዓለም አቀፍ ስምምነቶችን በማክበር በሰላም አብሮ መኖርና መልካም ጉርብትናን የሚያመጣ በመሆኑ አቀራረጹ ተገቢ መሆኑን አመልክተዋል ::

አቶ መሀሙድ ድሪር ከክልል 5 በበኩላቸው የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን የፌዴራሉን አባሎች የሚያጠቃልልና በዓለም አቀፍ ስምምነቶች መሠረት እንደሚወሰን የሚገልጸው አንቀጽ 2 ፌዴራላዊ ሆና የምትመሠረተው ኢትዮጵያ የፌደራሉ አባላት የሚኖሩበትን ሥፍራ የሚያጠቃልል መሆኑን ስለሚያመለክት የኢትዮጵያ መንግሥት ፌዴራላዊና ዲሞክራሲያዊ ሆኖ እንደሚዋቀር የሚገልጸው አንቀጽ 1 ጋር የጠበቀ ቁርኝት እንዳለው ፣ የፌዴራል አባላት ሲባልም ኤርትራን እንደማይጨምርና ኤርትራም የኢትዮጵያ አካል ያልሆነች ሉዓላዊ አገር መሆኗ መታወቅ እንዳለበት ፣ የኢትዮጵያ የግዛት ወሰንም ከኬንያ ፣ ከሶማሊያ ፣ ከጂቡቲ፣



ከኤርትራና ከሱዳን ጋር የሚዋሰን መሆኑን ማስረገጥ እንደሚገባ ገልጸው በተጨማሪም ኢትዮጵያ ከሌሎች አገሮች ጋር በሰላም ለመኖር እንዲያስችላት ዓለም አቀፍ ስምምነቶችን እንደምታከብር ስለሚገልጽ እንዳለ እንዲያልፍ የውሳኔ ሀሳብ አቅርበዋል ::

ከዚያም ለጉባኤው ሊቀመንበር አንቀጹ እንዳለ እንዲቀመጥ የደገፉት ሰዎች የተናገሩትን ጠቅሰው አጠቃላይ በአንቀጹ ላይ ተቃውሞ ወይም በአንቀጹ ላይ የተለየ ሀሳብ ያለው ማቅረብ እንደሚችል ገልጸዋል ::

በዚህም መሠረት አቶ ደስታ ቁናሳ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል የአንቀጹ አቀማመጥ እንዳለ መሆኑን ተቀብለው "የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን" ከሚለው ርዕስ ውስጥ "ግዛት" የሚለው ቃል ቢቱ በመወያየት በሌላ ቃል እንዲተካው ወይም በምትኩ "ዳር ድንበር" የሚለው እንዲቀመጥ አሳስበው ይህ ካልተደረገ ግን የኢትዮጵያ ሕዝቦች ራሳቸውን የሚያስተዳድሩ ሳይሆኑ እንደቀድሞው ሌላ ኃይል የሚገዛቸው እንደሚያስመስል አመልክተዋል ::

ቀጥሎም አቶ ዳንኤል በላይነህ ከክልል 14 በበኩላቸው የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን በዓለም አቀፍ ስምምነቶች መሠረት የተወሰነ መሆኑን ራሳቸውና የወከላቸው የክልል 14 ወረዳ 16 ሕዝብ እንደሚይቀበሉት ፣ የሚይቀበሉብትም የአንድ አገር ሕገ መንግሥት ሲቀረጽ አብዩ ተግባር የአገሪቱን አንድነት ፣ ወሰኗንና የሕዝቦቿን ሉዓላዊነት የሚያረጋግጥ መሆን ስላለበትና የኢትዮጵያ ሕገ መንግሥትም ይህንን ማድረግ ስለሚጠበቅበት እንደሆነ አመልክተው አባቶቻችንና አያቶቻችን ደማቸውን አፍስሰው አጥንታቸውን ከስክሰው ፣ ይህ ነው የማይባል መስዋዕትነት ከፍለው ለዚህ ለአንድነት ያበቋትን ኢትዮጵያ ይህ ሕገ መንግሥት ማስጠበቅ እንደሚኖርበት አሳስበዋል ::

አያይዘውም ያለው የሽግግር መንግሥት በሽግግር ወቅት ኢትዮጵያውያን ሳይመከሩበትና ሳይዘከሩበት የኢትዮጵያ አካል ለሆነችው ኤርትራ የመገንጠል ዕውቅና መስጠቱ አግባብ እንዳልሆነ በራሳቸውና በወከላቸው ወረዳ 16 ሕዝብ ዘንድ ተቀባይነት እንደሌለው ጠቅሰው በሕገ መንግሥቱ የሚቀረጸው ሕግ የኢትዮጵያን የግዛት ወሰን ሲያስቀምጥ ኤርትራን ብቻ ሳይሆን የቀይ ባህር ደሴቶችንም ጭምር መሆን እንዳለበት አመልክተዋል ::

ከዚያም አቶ ዘለሌ ፀጋሥላሴ ከክልል 14 የኢትዮጵያ የፌዴራል አባሎች የግዛት ወሰናቸውን ራሳቸው በፈቃዳቸው እንደሚወስኑ መገለጹን ፣ ይህ ግን እያንዳንዱ የፌዴራል አባል በፈለገው ጊዜ እየተነሳ የድንበር ወሰኔ ይህ ነው እንዲልና በአዋሳኝ ክልሎች መካከል የርስ በርስ ግጭት አስከትሎ ውስጣዊ ሉዓላዊነትን እንደሚያሳጣ፣ ይህ ከሚሆን የፌዴራል አባሎችን የድንበር ወሰን በሕገ መንግሥቱ ለይቶ ማስቀመጥ

እንደሚጠቅም ፣ በአንቀጽ 47 የተቀመጠው የፌዴራል አባሎች ዝርዝርም ወደ አንቀጽ 2 ተዛውሮ መቀመጥ እንዳለበት አሳስበው ኢትዮጵያ በአራቱም አቅጣጫዎች የምትዋሰናቸው ጎረቤት አገሮች በስም ተጠቅሰው በአንቀጹ ውስጥ መካተት እንዳለባቸው ገልጸዋል ።

አቶ መሐመድ ጣሂር ከክልል 5 ደግሞ በሰጡት አስተያየት ከዚህ በፊት የነበረው የወሰን አከላለልና የአገር አንድነት የተባለው በሕዝቦች ፍላጎት የመጣ ሳይሆን በኃይልና በጉልበት እንደነበር ፣ በዚህ ምክንያትም ኢትዮጵያ ለስቃይ መዳረጓን ፣ ያለፈውን አከላለል እንተበል ማለት ያለፈውን ስቃይ መድገም እንደሚሆን ገልጸው በአንቀጽ 2 የተቀመጠው የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን የኢትዮጵያ ብሔር / ብሔረሰቦችና ሕዝቦች የሚያንፀባርቅና ኢትዮጵያዊነትም በፍላጎትና በመፈቃቀድ ላይ የተመሠረተ እንደሆነ የሚያመለክት ስለሆነ ተገቢ እንደሆነ ፣ ኤርትራ የተገነጠለችው በሕዝቧ ፍላጎት በመሆኑ የዚያን ሕዝብ መብት መግፋት አገሪቱን ወደ ጦርነትና ወዳልተፈለገ መጥፎ ሁኔታ እንደሚከታት አሳስበዋል ።

በማስከተልም የጉባኤው ሊቀመንበር የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን የሚለው አንቀጽ 2 በተመለከተ ግዛት የሚለውም ቃል እንዲቀየር ወይም በሌላ ቃል እንዲተካ የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን አከላለል የአገሪቱን አንድነት የሚያስጠብቅና ኤርትራን ምየሚጨምር መሆን እንዳለበት ፣ በአንቀጹ የክልሎች ወሰንና ዝርዝራቸው መቀመጥ እንደሚገባው ፣ እና የኢትዮጵያ ጎረቤት አገሮች በስም ተጠቅሰው በአንቀጹ መግባት እንዳለባቸው አስተያየቶች መዘንዘራቸውን ገልጸው ጉዳዩ የሚያወያይ ከመሆኑ አንፃር ተጨማሪ ውይይት ስለሚያስፈልገው አስተያየቶች እንዲቀርቡ ቤቱን ጋብዘዋል ።

በዚህም መሠረት አቶ ግርማ አዱኛ ከክልል 4 ባለፉት መንግሥታት የነበረው የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን አከላለል በሕዝቦች ፈቃድ ላይ ያልተመሠረተ ገገሮዎች ለአስተዳደር እንዲያመቻቸው ብቻ ተደርጎ የተቀመጠ ስለነበረ ለዘመናት በሕዝቦች መካከል ደም መፋሰስ እንዲኖር ፣ አያሌ ንብረት እንዲወድም ምክንያት እንደሆነ ገልጸዋል ።

አስከትለውም የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን ከታሪክ ጋር ማያያዝ በራሱ ፋይዳ እንደሌለውና ተግባራዊ የሚሆነውም ሕዝቦች አምነውብትና ፈቅደው ሲከለል እንደሆነ ገዥዎችና ትምክህተኞች ኢትዮጵያ ከራስ ካሳር እስከ ራስ ዲሚራ እንደምትዘረጋ ቢናገሩም በሕዝቦች አለመፈቃቀድ ምክንያት በደረሰው ሽኩቻ ለደቀቀው ኢኮኖሚ መፍትሔ ሊያመጣ እንዳልቻለ ፣ የኢትዮጵያ ሕዝቦች በአንድነት ፣ በእኩልነት ፣ በመተማመንና በመረዳዳት ፣ በደስታና በተድላ መኖር የሚችሉበት ሁኔታ ሊመጣ የሚችለው የሕዝቦችን ፈቃድ ከግምት ውስጠ ያስገባው አንቀጽ 2 እንዳለ ሲቀመጥ



እንደሆነ ፣ ይህንን የማይቀበሉ ቢኖሩ ካለፈው ታሪካቸው መማር የማይፈልጉ ትምክህተኞችና ጠባቦች ብቻ እንደሆኑ አስገንዝበዋል ።

ቀጥለውም በቀደሙት ሥርዓቶች ኢትዮጵያ የዓለም አቀፍ ስምምነቶችን የማታከብር በመደረጓ ሕዝቦቿ ከጎረቤት አገሮች ጋር የነበራቸው ግንኙነት የወንድማማችነት ሳይሆን በጥርጣሬ የመተያየት እንደነበረ ፣ ከሶማሊያ ጋር በተካሄደው ጦርነት አያሌ ሕዝቦች ያለቁትም በዚህ ምክንያት እንደሆነ ፣ የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን ኤርትራንና ቀይ ባህርን ያጠቃልላል የሚለው አባባልም አሮጌ ታሪክን ይዞ መንገታገትና ኤርትራም የተገነጠለችው ሕዝቧ በደረሰባቸው ስቃይ መሆኑን መርሳት እንደሚሆን ያብራሩ ሲሆን ኢትዮጵያ ከጎረቤት አገሮች ጋር ያለ እንዳች ሥጋት ጉርብትናዋን እንድትቀጥል ከተፈለገ በአንቀጹ የተቀመጠው ተግባራዊ መሆን እንደሚኖርበት አመልክተዋል ።

በማስከተልም አቶ ተስፋዬ ፉቻላ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል የኢትዮጵያ ሕዝቦች ትክክለኛ ትርጓሜው ተነፍጎት እንደቆየ ፣ የኢትዮጵያ ዳር ድንበርም ከተስፋፊዎች ታሪክ ጋር ተቆራኝቶ እየተለጠጠ ፣ ሕዝቦች ብሔራዊና ሰብአዊ ሕልውናቸው ተገፍፎ ለጅምላ እልቂት ተዳርገው የአገሪቱ የግዛት ወሰንም እስከ እዚህ ነው ብሎ መወሰን እማይቻልበት ደረጃ ተደርሶ እንደነበር ገልጸዋል ።

አያይዘውም የአንድ አገር የግዛት ወሰን እስከየት እንደሆነ ከመናገር በፊት በቅድሚያ በዚያ የግዛት ወሰን ውስጥ አብሮ ለመኖር ያለውን ፈቃደኝነትና የመሬት ባለቤትነት ማረጋገጥ እንደሚገባ ፣ ሕዝቡ አብሮ ለመኖር የሚፈልገውም መሠረታዊ መብቶቹ ሲታወቁለትና ሲከበሩለት እንደሆነ ፣ ከዚህ ውጭ ያለ ሕዝቦች ነፃ ፈቃድ ብሔራዊ አስተዳደርን በመጨፍለቅ ግዛቴ ነው የሚለው አካሄድ የትም እንዳላደረሰ፣

በዚህ ረገድ የአንቀጽ 2 ድንጋጌ የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን የኢትዮጵያ ሕዝቦች አብሮ የመኖር ነፃ ፈቃድ ከግምት ውስጥ ያስገባና የዓለም አቀፍ ድንጋጌዎችን መሠረት ያደረገ በመሆኑ የኢትዮጵያ ሕዝቦች የሌሎች አገሮችን ዳር ድንበር የሚያከብሩ ሕግና ሥርዓት የሚገዛቸው መሆኑን ስለሚያመለክት እንዳለ ቢያልፍ እንደሚጠቅም አብራርተዋል ።

አክለውም የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን ኤርትራን ይጨምራል የሚለውን አገላለጽ መጠቀም ዲሞክራሲያዊ መብት ቢሆንም ባለፈው ሥርዓት ይህን መሰል የመስፋፋት ፖሊሲ ሰለባዎች ለሆኑ ሕዝቦች ግን ለጆሮ የሚቀፍ መሆኑን እንደ ደቡብ ሕዝቦች ተወላጅነታቸው አስገንዝበዋል ።

በመጨረሻም የኢትዮጵያ የፌዴራል መንግሥት አባላት ዝርዝር በአንቀጽ 47 የተቀመጠው እንደሚበቃና ወደ ጠቅላላ ድንጋጌ አንቀጽ 2 ውስጥ ማምጣት

እንደሚያስፈልግ ጠቅሰው "ግዛት" የሚለው ቃልም የመስፋፋት ስሜትን የሚገልጽ በመሆኑ "ተሪተሪ" ወይም "ባውንደሪ" የሚለውም የእንግሊዝኛ ቃል የሚተካ ከተገኘ "ግዛት" የሚለውቃል ቢለወጥ እንደሚስማሙ ገልጸዋል ::

ቀጥሎም ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ከክልል 5 "ግዛት" የሚለው ቃል ተሪተሪ የሚለው ቃል መተኪያ እንደሆነና ብዙም እንደማያከራክር ጠቁመዋል ::

አያይዘውም አቶ ዳንኤል በላይነህ ከክልል 14 ወረዳ 16 የሚሰነዝሩት ሃሳብ የወከላቸው ሕዝብ ሀሳብም እንደሆነ ሲናገሩ የወከላቸውን ሕዝብ ብዛትም ቢናገሩ ለሀሳባቸው ክብደት ሚዛን እንደሚረዳ አሳስበው ከክልል 5 የመጡት ጉባኤተኞች እያንዳንዳቸው ከ13 ሺህ በላይ በሆነ ሕዝብ ተመርጠው እንደተላኩና በአንፃሩ ግን አቶ ዳንኤል በላይነህ ወካይ ሕዝብ ቁጥር 6981 እንደሆነ ጠቁመዋል ::

ቀጥለውም የአንድ አገር የግዛት ወሰን መከለል ያለበት ከዚህኛው እስከ እስከዚያኛው ተራራ የሚዘረጋ መሬት አለኝ በሚል ሳይሆን ሕዝቦች ተፈላልገውና ተፈቃቅደው የሚመሠረቱት ፣ የመሬት ስፋት ሳይሆን የሕዝቦች ፍላጎት ቅድሚያ ተሰጥቶት መሆን እንዳለበት አሳስበው የኢትዮጵያ ዳር ድንበር እስከ ሕንድ ውቅያኖስ ወዘተ... ይዘረጋል የሚለው ለክት የለሽ ምኞት በደርግና ከደርግ በፊት የነበረው ችግር አሁን የተጀመረው የተስፋ ወቅት መልሶ እንደሚያጨልምና ለዳግም ችግር የሚዳርግ እንደሆነ አስገንዝበው ያለፈውን መሬት የማስቀደም የዳር ድንበር አወሳሰን እንከተል የሚሉ ሰዎች ራሳቸውን ችግር ውስጥ እንዳይከቱ አስጠንቅቀዋል ::

የኤርትራን መገንጠልን በተመለከተ ኤርትራን ያስገነጠላት የሽግግሩ መንግሥት ሳይሆን በኖቬምበር 1974 ዓ.ም ጀኔራል አማን አምዶምን ገድሎ የኤርትራን ሕዝብ ያስኮረፈው የደርግ መንግሥት እንደሆነ ጠቅሰው ከዚያ በፊት በሁለቱ የኤርትራ ነፃ አውጪ ግንባሮች ተሰልፎ የነበረው የኤርትራ ሕዝብ ቁጥር ከ4000 /ከአራት ሺህ / የማይበልጥ እንደነበር አስታውሰው ጀኔራሉ በተገደሉ ስድስት ወር ባልሞላበት ጊዜ ውስጥ ግን ሁለቱ ግንባሮች ከ25 ሺህ ያላነሰ ደጋፊ ከጎናቸው ማሰለፍ እንደቻሉ ተናግረዋል ::

አያይዘውም የሽግግሩ መንግሥት ከመቋቋሙ ጥቂት ቀደም ብሎ የትኛው የኤርትራ ክፍል ይቆጣጠር ነበር ? ሲሉ ጠይቀው በአሁኑ ሰዓት ኤርትራ ተገነጠለች ማለት መሬቷ ቦታውን ለቆ ሄዷል ማለት እንዳልሆነና በሁለቱ ሕዝቦች መካከል ከተፈጠረው መልካም ግንኙነት አንፃርም እንደገና አንድ ላይ የመሆን ተስፋ ከፍተኛ መሆኑን ጠቅሰው የመልካም ግንኙነት ሁኔታ ሲያስረዱም ከ3 ዓመት በፊት የሻከረ ግንኙነት የነበራቸው ሕዝቦች በአሁኑ ጊዜ በሁለቱም ወገን 90% የሚሆነው ሕዝብ



መልካም ግንኙነት እንደሚፈልግ 10% ቢሆን ቅንነት ለጎደላቸውና መጥፎ አስተሳሰብ ላላቸው እንደሚተዉት ጠቁመው ይህ ሊሆን የቻለው እንደበፊቱ በጉልበት ሳይሆን በመፈቃቀድ አብሮ የመኖርኑ ዕድል በማመቻቸት እንደሆነ ፣ ቢነይል ከሆነ ግን እንኳን ኤርትራን ክልል 5ም አብሮ የመኖር ዕድሉ የጠበበ እንደሚሆን አስገንዝበዋል ::

ማብራሪያቸውን በመቀጠልም ባለፉት ሥርዓቶች የሚፈለገው የሶማሌ ሕዝብ የሚኖርበት መሬት እንጂ ራሱ ሕዝቡን ባለመሆኑና ሶማሌ ሲባልም እንደ ኢትዮጵያዊ የሚቆጠር ስላልነበረ ከግማሽ በላይ የሚሆነው ለስደት ተዳርጎ እንደኖረ፣በአሁኑ ሰዓት ግን አብሮ ለመኖር አመቺ ሁኔታ በመፈጠሩ ከ95% በላይ የሚሆነው የሶማሌ ሕዝብ ከሌሎች ኢትዮጵያውያን አብሮ ለመኖር ዝግጁ መሆኑን አረጋግጠው እንደቀድሞ መሬታችሁን እንጂ ሶማሌዎችን አንፈልጋችሁም የሚል ከመጣ እንደ ኤርትራ ክልል 5ም ገፍቶ ማስወጣት እንደሆነ አመልክተዋል ::

አክለውም አባቶቻችን ለኢትዮጵያ አንድነት የመታገላቸው ታሪክ ሲወሳ ሶማሌና አሮሞ እንዳልታገለ እንደሚቆጠርና የደቡብ ሕዝቦች ደግሞ በትግሉ ጭራሽ ስማቸው እንደማይነሳ ፣ ሐቁ ግን ይህ ሳይሆን በደበልጥ የታገሉት ሶማሌዎችና ሌሎች ሕዝቦች እንደሆኑና ለዚህም እነደጃዝማች ዑመር ስመተርን መጥቀሱ እንደሚበቃ ገልጸው በወልወል ጦርነት ለወደቁት ሐውልት ሲሠራ ለዕውነተኛ ታጋዮች ሳይሆን ሸሽተው ሲያመልጡ በአውሮፕላን ተመተው ለሞቱት እንደሆነ ጠቁመዋል ::

አስከትለውም በትናንቱ ጀግንነት ዛሬ መኖር እንደማይቻልና የጊዜው የጀግንነት መለኪያ ጦር ማንሳት ሳይሆን የውስጥ ችግሮችን አስቀድሞ መፍታት እንደሆነ ፣ የወሰን ጥያቄ በሕዝብ ፍላጎት የሚመለስ መሆኑ ገና ኢትዮጵያ እስከ ጂቡቲ ፣ ሶማሊያ ወዘተ... ትዘረጋለች የሚለው ሕልምም የሁሉም ሕልም ቢሆንም ተግባራዊነቱ ግን ከሕዝብ ፈቃድ ውጭ ስለማይታሰብ ሕልሙን ቀንሶ የውስጥ ግንኙነትን ማጥበቅ እንደሚሻል ገልጸዋል ::

ቀጥሎም አቶ ሀሰን አሊ ከክልል 4 የኢትዮጵያ የግዛት ወሰንን በሚመለከት ሁለት አበይት ጉዳዮች ማለትም ኢትዮጵያ ከዚህ ቀደም የገባቻቸውን ዓለም አቀፍ ስምምነቶች መከበርና የውስጥ የድንበር ወሰኑ አከላለልም በሕዝቦች ፈቃድ ላይ ተመሥርቶ መሆን እንዳለበት በአንቀጽ 2 መገለጹን ጠቁመው ኢትዮጵያ የአፍሪካ አንድነት ድርጅትና የተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ቻርተሮችን ፣ ከጎረቤት አገሮች ማለትም ከኬንያ ፣ ከሱዳን ፣ ከኤርትራ ፣ ከጂቡቲና ከሶማሊያ ጋር ውሎችን እንደፈረመች ገልጸው እነዚህን ውሎች ተቀብላ ካለፀደቀች ኢትዮጵያን ለዓለም አቀፍ ሕግና ሥርዓት የማትገዛ የአገሮችን ሉዓላዊነት የማታከብር አድርጎ ስለሚያስቆጥራት ከዓለም የመገለል አደጋ አስከትሎ የሚጎዳው እኛኑ ራሳችን ነው ሲሉ አስገንዝበዋል ::

የክልሎችን ጻር ድንበር እዚሁ በጉባኤው ይወሰን በሚል የተሰነዘረው አስተያየትን አስመልክተው የክልሎችን ጻር ድንበር የሚወስነው ባለቤቱ የክልሉ ሕዝብና የሚወክለው የክልል ምክር ቤት እንጂ ጉባኤው አዳራሽ ውስጥ ሆኖ የኦሮሚያን ክልል ፣ የክልል 5 ወዘተ… ወሰን እስከዚህ ድረስ ብሎ መወሰን እንደማይቻል አመልክተው በክልሎች መካከል አለመግባባት ከተፈጠረም ሊፈታ የሚችልበት መንገድ በዚሁ ረቂቅ ሕገ መንግሥት በሌላ አንቀጽ ስለተቀመጠ ስለጉዳዩ ሲደረስበት መወያየት እንደሚቻል ጠቁመዋል ።

አስከትለውም ስለኤርትራና ከኤርትራ ጋር ስለተያያዘ ታሪክ ማውሳት ከርዕሰ ጉዳዩ መውጣት ቢሆንም በዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን የተነገረውን ግን መስተካከል እንዳለበት ፣ የኤርትራ ሕዝብ ለመገንጠል ያበቃው ዋናው ምክንያት የጀኔራል አማን አምዶም በደርግ መገደል ሳይሆን ኤርትራዊያን ለዲሞክራሲያዊ መብታቸው ያደረጉት የትግል ውጤት መሆኑን አስገንዝበው በፌዴሬሽን ጊዜ የፌዴሬሽኑ ውህደት እንደግፍ በመቆጠር ፣ የፌዴሬሽኑም ውህደት ሂደትም ዲሞክራሲያዊ ባለመሆኑ አንቀበልም ያሉ ኤርትራዊያን እንደነበሩ አስታውሰው የሕዝቦች ለዲሞክራሲያዊ መብት መታገል ከአንድ ግለሰብ መሾም ፣ መሻር ወይም መሞት ጋር ማያያዝ ስህተት ስለሆነ ሊስተካከል እንደሚገባው አሳስበዋል ።

ቀጥሎም አቶ ዳንኤል በላይነህ ከክልል 14 የወረዳ 16 ሕዝብ አቋሙን እንዳንፀባርቅ መርጦ ልኮኛል ሲሉ የተናገሩትን አስመልክተው አቶ ሁሴን አሊ በሰጡት አስተያየት አቶ ዳንኤል በላይነህ ኢትዮጵያ ዓለም አቀፋዊ ስምምነቶችን እንዳትቀበልና ብሎም የጎረቤት አገሮችም ሉዓላዊነት እንዳታከብር በመናገር የጦርነት ጥሪ እንዳስተጋቡና ይህም ደግሞ የወረዳ 16 ሕዝብ አቋም ሊሆን እንደማይችል ገልጸው ሕዝቡ ወክሎኛል በሚል ስም ወደ ተሳሳተ መንገድ መራመድ ተገቢ እንዳልሆነ አመክተዋል ።

ከዚያም አቶ አባይ ፀሐዬ ከክልል 1 " የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን የፌዴራሉን አባሎች ወሰን የሚያጠቃልል ሆኖ በዓለም አቀፍ ስምምነቶች መሠረት የተወሰነ ነው ። " የሚለው አንቀጽ 2 ባለፉት ሥርዓቶች ከነበረው የግዛት ወሰን አከላለልና አመለካከት መሠረተ ሀሳብ የተለየ ፣ የአገርን አንድነት በፅኑ መሠረት ላይ በማቆም መበታተንና መከፋፈልን የሚያስቀር ፣ በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ከተካተቱና ሥር ነቀል ለውጥ ያመጣሉ ተብለው ከሚገመቱት አንቀጾች መካከል አንዱ እንደሆነ ገልጸው የዓለም አቀፍ ስምምነቶች እንዲከበሩ በመደንገጉም ሰላም በአገር ውስጥ እንዲሰፍን ብቻ ሳይሆን ከአጎራባች አገሮች ጋር ያለው ግንኙነትም በመልካም ግንኙነት ላይ የተመሠረተ በጦርነት ከመፈላለግ የሚያድን እንደሆነ አስገንዝበዋል ።



አያይዘውም ከዚህ ቀደም የነበሩት የድንበር አከላለሎች ሕዝቦች ፈቅደው ኢትዮጵያውያን ነን ብለው በወሰኑት ሳይሆን አንድ ንጉሥ ወይም ፊተውራሪ ከነሠራዊቱ ተንቀሳቅሶ ሊደርስ የቻለበት መሬት እንደነበር ፣ ይህም በኃይል የተያዘው ሕዝብ እምቢ አልገዛም ሲል በጦርነት ለማሳመን በተደረገው ጥረት ከሰላም ይልቅ ጦርነት ከአንድነት ይልቅ መበታተን በአገሪቱ ሰፍኖ እንዲኖር እንዳደረገ ገልጸዋል ።

አክለውም በአንቀጽ 2 መሠረት ግን ሕዝቦች ፈልገው ኢትዮጵያውያን ነን ያሉበት ሥፍራ ሁሉ የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን እንደሚሆን መቀመጡን ይህም ወሰን አከላለል መነሻው መሬት ሳይሆን ነዋሪው ሕዝብ መሆን እንዳለበት የሚተብል ፣ ሕዝቡ ፈቅዶ እስከገባ ድረስም በግድ ኢትዮጵያዊ ሁን ብሎ ጦር ከመምዘዝ ሥጋት እንደሚያድን ጠቅሰው ሕዝቦች ፈቅደው ኢትዮጵያውያን ነን ካሉ ማንም ኃይል ኢትዮጵያውያን አይደላችሁም ሊላቸው ወይም ኢትዮጵያውያን መሆን አንፈልግም ካሉም ማንም ኃይል በግድ ኢትዮጵያውያን ሊያደርጋቸው የማይችል መሆኑ ሊታወቅ እንደሚገባ አስገንዝበዋል ።

አቶ አባይ ፀሐዬ ማብራሪያቸውን በመቀጠልም ሕዝቡ ኢትዮጵያዊ ነኝ እንዲል ማድረግ የሚቻለው ልማትን በማሳደግ ፣ ፍትሕን በማስፈንና መብትን በማስከበር የኢትዮጵያዊነት መንፈስና ፍቅር በማሳደር እንጂ የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን እስከ ቀይ ባህር ወዘተ… ነው ብሎ በሕግና በሕገ መንግሥት በመደንገግ ወይም በጋዜጣ ላይ በመጻፍ አለመሆኑና ሕዝቡን በግዴታ ጎትቶ ማምጣትም ሆነ አንድነትን ማስጠበቅ የማይቻል መሆኑ የ30 ዓመት ተመክሮ እንዳረጋገጠ ጠቅሰው በአንቀጽ 2 የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን የፌዴራል አባሎች ወሰን ተብሎ መጠቀመጡ ካለፈው ስህተት ለመዳን እንደሆነ ገልጸዋል ።

አስከትለውም የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን የፌዴራል አባሎች ወሰን እንዲሆን መደረጉ ለአንድነት ፅኑ መሠረት ከመጣሉም በተጨማሪ ሕዝቦች ተፈቃቅደውና ተከባብረው ለመኖር የሚችሉበትን ሁኔታ እንደሚያመቻች ፣ አለበለዚያ ግን የመበታተን አደጋ ስለሚከተል ለመጠንቀቅ በማዕከላዊ መንግሥት ለአስተዳደሩ በአጠቃላይ ለኢትዮጵያ ሕዝብ ትምህርት እንደሚሰጥ አስገንዝበዋል ።

ቀጥለውም የሽግግር መንግሥቱ የፈረማቸው ዓለም አቀፍ ስምምነቶች ሕዝቡ ሳይመክርበት የተፈረሙ በመሆናቸው ተቀባይነት የላቸውም የሚል ሀሳብ እንደቀረበ ፣ ሆኖም አፄ ሚኒሊክ ሆኑ አፄ ኃይለ ሥላሴ ስምምነቶችን ሲፈርሙ ሕዝቡን ስላላማከሩ ላለመቀበል የቀረበው ሀሳብ ስህተት እንደሆነ ፣ በተጨማሪም የአንድን ሕዝብ ዕድል ራሱ ሳይሆን ሌላው ይወስንለት የሚለው መሠረተ ሀሳብ የተሳሳተና የተዛባ አገላለጽ

መሆኑን ጠቅሰው አብዛኛው የኢትዮጵያ ሕዝብ ግን በሌላ ሕዝብ ላይ ለመወሰን በጦርነትና በኃይል ረገጣ ልግዛ የሚል እንዳልሆነ አመልክተዋል ፡፡

ከዚህ አንፃር የኤርትራ ሕዝብ የራሱን ዕድል በራሱ መወሰኑና የሽግግር መንግሥትም የሪፈረንደሙን ውጤት መቀበሉና ስምምነቶችን ከኤርትራ ጋር መፈረሙ የሕዝቦችን የዲሞክራሲ መብት መሠረተ ሀሳብ የተከተለ ፣ በጊዜው ያለው መንግሥት ስምምነቶችን መፈረም ያለበት መሆኑን ከሚያመለክተው የኢትዮጵያ ታሪክ እና ከዓለም አቀፍ ስምምነቶች አፈራረም ሥርዓት ጋር የተስማማ እንደሆነ ገልጸዋል ፡፡

አክለውም የክልልችን ስም ዝርዝርና ወሰን በአንቀጽ 2 እንዲገባ የቀረበውን ሀሳብ አስመልክተውም በሕገ መንግሥቱ የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን የፌዴራል አባሎች ወሰን " የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን የኢትዮጵያ አካል እንሆናለን የሚሉት የፌዴራል አባሎች የሚለው ሕዝቦች ክልል ነው ፡፡" የሚለው እንደሚበቃ ፣ ከዚህ ውጭ ግን የእያንዳንዱ ክልል ጠረፍ ፣ ወንዝ ፣ አካባቢ ወዘተ... በስም በአንቀጹ ውስጥ መዘርዘር እንደማይቻል፣ የፌዴራል አባሎች ዝርዝርም የመንግሥት አወቃቀር በሚለው አንቀጽ ሥር እንደተቀመጠ ፣ ወደ አንቀጽ 2 ማምጣቱም እንደማያስፈልግ ጠቅሰው ለኢትዮጵያ አንድነትና ሰላም ሲባል አንቀጽ 2 እንዳለ ጉባኤው እንዲያፀድቃ አሳስበዋል፡፡

ከዚያም አቶ ዳንኤል በላይነህ ከክልል 14 ሀሳባቸውን የሚያቀርቡት የመረጣቸውን የወረዳ 16 ሕዝብ አስተሳሰብ ወክለው እንደሆነ በመግለጻቸው የወረዳው ሕዝብ ቢመርጣቸውም ጠቅላላ አመለካከቱን ሊወክሉ ስለማይችሉ በወረዳው ሕዝብ ስም መናገር ከሥነ ሥርዓት ውጭና የነዋሪዎቹን መብትም መጋፋት እንደሆነ ከጉባኤው ሊቀመንበር ማሳሰቢያ ተሰጥቷቸዋል ፡፡

አቶ ዳንኤል በላይነህ ከክልል 14 የፌዴራል አባሎች ዝርዝር በአንቀጽ 2 መካተት አለበት ያሉበትን ምክንያት ሲያስረዱም ዝርዝራቸው ካልተጠቀሰ አንዱ ክልል የሌላውን ቆርሶ የመውሰድ ችግር እንደሚመጣና በቅርቡም የጎንደር አካል የሆነው ሰቲት ሁመራ ተቆርሶ ወደ ትግራይ ክልል እንዲገባ እንደተደረገ ገልጸዋል ፡፡

የጉባኤው ሊቀመንበር የተጠቀሰው የክልሎች ጉዳይና በክልሎች የሚፈታ በመሆኑ ስለ ጉዳዩ መናገር ከአርዕስት መውጣት መሆኑን አመልክተዋል ፡፡

ከዚያም አቶ ዳንኤል በላይነህ ማብራሪያቸውን በመቀጠል በፊት ኢትዮጵያውያን አባቶቻችንና አያቶቻችን ደማቸውን አፍስሰው አጥንታቸውን ከስክሰው የኢትዮጵያን አንድነት ማስከበራቸው ሐቅ እንደሆነ ሲናገሩ ሁሉም የኢትዮጵያ ሕዝቦች መታገላቸውን እንደገለጹ አውስተው ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ግን ሶማሌ ፣ ኦሮሞና ደቡብ ሕዝቦች እንዳልታገሉ ተቆጥረዋል በማለት መናገራቸው ያልተባለውን እንደሆነና



ይህም እንዳሳዘናቸው ገልጸው የሚያንጸባርቁት ሀሳብ የጦርነት ጥሪ ያዘለና ወክለኝ የሚሉት የወረዳ 16 ሕዝብ አስተሳሰብ ሊያንፀባርቅ የማይችል እንደሆነ በአቶ ሀሰን አሊ ከክልል 4 ለተሰነዘረው አስተያየት ሲመልሱ የወረዳ 16 ሕዝብ ከአቶ ሀሰን አሊ ይልቅ ራሳቸው እንደሚያውቁትና አውቋቸውም እንደመረጣቸው አመልክተዋል ፡፡

ቀጥለውም ለኢትዮጵያ አንድነት እንታገላለን እያሉ የሚያወሩት ነፍጠኞችና ጠባቦች እንደሆኑ የቀረበውን አስተያየት አስመልክተውም ሲናገሩ ነፍጠኛ ወይም በሌላ ስያሜ ቢጠራም ለኢትዮጵያ አንድነት ከታገለ ሐቀኛ ኢትዮጵያዊ ነው ብለው እንደሚያምኑና ጠባብ ብሎ ሌሎችን ከመስደብ በፊት በቅድሚያ እኔ ማን ነኝ ? ብሎ ራስን መጠየቅ እንደሚገባ ፣ አስተምራ ለወግ ለማዕረግ ያበቃችን አገር ስለአንድነቷ አለማሰብ የበሉትን ወጭት ደፋ እንደሆነ ገልጸዋል ፡፡

ከዚያም አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 በጉባኤው አባቶቻችንና አያቶቻችም ያቆዩትን ታሪክ መጠበቅ እንዳለበት በተደጋጋሚ እንደተነገረና ከአባቶቹና ከአያቶቹ ሳይማር ለሥልጣኔ የበቃ ሕዝብ ቢታሪክ ስላልታየ የሚለው አባባል ተገቢ ቢሆንም ከአባቶች የወረስነው ታሪክ ግን ጠቃሚነቱና ጎጂነቱ እየታየ እንጂ ሁሉንም በጅምላ እንቀበል ማለት የትም እንደማያደርስ ፣ ለምሳሌም አሜሪካውያን ከአባቶቻቸው ጥሩውን ወስደው መጥፎውን እየጣሉ ባያልፉ ኖሮ በአሁኑ ሰዓት የዓለም ዲሞክራሲና ኢኮኖሚ ብልፅግና ምሳሌ መሆናቸው ቀርቶ እንደአባቶቻቸው የባሪያን ንግድ የሚያካሂዱ ይሆኑ እንደነበር ፣ ከዚህ አንፃር የኢትዮጵያ ታሪክ ሲወሳ አባቶች የሕዝብን መብት ሲረግጡ የነበረ ቢሆንም እኛም እነርሱን እንከተል ማለት እንደሚያስኬድ አብራርተዋል ፡፡

አክለውም የኤርትራን ሁኔታ በተመለከተም ኤርትራ ከአፄ ሚኒልክ እስከ አፄ ኃይለ ሥላሴ የመጀመሪያ የንግሥና ዘመናት የኢትዮጵያ አካል እንዳልነበረች ፣ በዚህ ሁኔታ በአባቶቻችንና በአያቶቻችን ጊዜ ኤርትራ የኢትዮጵያ አካል ነበረች ተብሎ አስተያየት ሲሰጥ የትኞቹ አያቶችና አባቶች የሚለውን ለይቶ ማመልከት እንደሚገባ አሳስበው የኤርትራ ሕዝቦች ራሳቸውን ነፃ ያወጡት ግንቦት 16ቀን 1983 ዓ.ም ሲሆን ደርግ ተሸንፎ ሥልጣን የለቀቀው ግን ግንቦት 20 ቀን 1983 ዓ.ም መሆኑ እየታወቀ ሳይቋቋም ለተፈጸመው ድርጊት የሽግግር መንግሥቱ ኤርትራን እንዳስገነጠለ አድርጎ ማውራት አግባብ እንዳልሆነ አስገንዝበዋል ፡፡

አያይዘውም በፌዴሬሽኑ ወቅት አንድነትን የሚፈልገውና መነጠል የመረጠው የኤርትራ ሕዝብ ሲታይ እኩል 50% በ 50% ያህል እንደነበረ መገመቱንና ከ30 ዓመታት ትግል በኋላ ግን በሪፈረንደሙ 99.9% መገንጠልን መምረጡንና ከሕዝቡ ይልቅ መሬቱን በመፈለግ የኃይሌሥላሴና የደርግ መንግሥታት ባካሄዱት ጭፍጨፋ

ምክንያት እንደሆነ ፣ የሪፈረንደሙም ውጤት ዓለም ከመሰከረለት በኋላ የሽግግር መንግሥቱ አግራብ የሕዝቡን ውሳኔ ተቀብሎ ስላምን ማስፈን እንደነበረ አስረድተዋል ።

አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ማብራሪያቸውን በመቀጠልም የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን ኤርትራንም እስከ ቀይ ባህር ድረስ ያጠቃልል ሲባል ኤርትራ እንዴት ልትመጣ እንደምትችል ከዚህ ቀደም ከነበረው የጦርነት አግራብ የተለየ ተግባራዊ ዘዴ መጠቆም ካልተቻለ አባባሉ ባዶ ሕልም እንደሚሆን ፣ ከተወሰነ ጊዜ በኋላ የኤርትራ ሕዝብ በፈቃዱ ይመለሳል የሚል የግል ዕምነት እንዳላቸው ገልጸዋል ።

በማስከተልም የክልሎች ዝርዝር በአንቀጽ 2 ይቀመጥ ለተባለውም የክልሎች ዝርዝር በመንግሥት አወቃቀር ሥር መግባት ስላለበትና በዚያም ሰፍሮ እንደሚገኝና ወደ ጠቅላላ ድንጋጌ ውስጥ መምጣት እንደማያስፈልገው አመልክተዋል ።

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር በአንቀጽ 2 ላይ በቂ ውይይት እንደተካሄደበት ገልጸው በተነሱት ነጥቦች ላይ ውሳኔ እንዲሰጥበት ለቤቱ አቅርበዋል ።

በዚህም መሠረት የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ የኢትዮጵያ የግዛት ወሰንን በተመለከተ የተሰነዘሩትን አስተያየቶች ሲያጠቃልሉም ፣

. የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን ኤርትራንና በቀይ ባህር የሚገኙትን ደሴቶችንም እንዲያካልል ፣

. የኢትዮጵያ ፌዴራል አባሎች ዝርዝርና ድንበር እዚሁ በጉባኤው ተወስኖ በአንቀጹ ውስጥ እንዲካተት ፣ እና

. " ግዛት " የሚለው በሌላ ቃል እንዲተካ

የሚሉ እንደሆኑ አመልክተው በእነዚህ ጉዳዮች ላይ በሁለቱም ወገን በቂ ውይይትና ክርክር የተካሄደ ስለሆነ በቀረቡበት ቅደም ተከተል መሠረት ውሳኔ እየተሰጠ እንዲታለፍና በመጨረሻም በአጠቃላይ አንቀጹ ላይ መወሰን እንደሚጠቅም አሳስበዋል ።

በዚህም መሠረት የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን ኤርትራንና በቀይ ባህር የሚገኙትን ደሴቶችንም ማካለል አለበት የሚለው ለድምፅ ቀርቦ ድጋፍ 2 ፣ ተቃውሞ 526 ፣ ድምፀ ተአቅቦ 5 በመመዝገቡ ሀሳቡ ተቀባይነት ሳያገኝ ቀርቷል ።

ቀጥሎም "ግዛት" የሚለው ቃል ተቀይሮ በሌላ ቃል እንዲተካ የቀረበውን ሀሳብ ተጨማሪ ውይይት ማድረግ አስፈላጊ ከሆነ አስተያየት ሊቀርብ እንደሚችል የጉባኤው ሊቀመንበር አመልክተዋል ።

በዚሁ መሠረት አቶ ዑመር አብዱላታር ከክልል 13 "ግዛት" የሚለው ቃል "ዳር ድንበር" በሚለው እንዲተካ ሀሳብ አቅርበው እንደነበር አውስተው ሆኖም "ዳር ድንበር"



የሚያመለክተው መሬትን ብቻ ሲሆን ግዛት የአየር ክልልንም የሚያጠቃልል በመሆኑና በሕገ መንግሥቱም ደግሞ ሰፋ ያለ ዕንስ ሐሳብ የሚያመለክት ቃልን መጠቀም ስለሚሻል ሳይቀየር እንዳለ ቢቀመጥ እንደሚመረጥ ገልጸዋል ።

አቶ ማሞ ገድቦ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል በበኩላቸው "የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን " ከሚለው ውስጥ "ግዛት" የሚለው ቃል ወጥቶ "የኢትዮጵያ ወሰን" በሚል ብቻ እንዲቀመጥ ወይም "ግዛት"በ"አስተዳደር" ተተክቶ "የኢትዮጵያ የአስተዳደር ወሰን" እንዲባል የሚሉ ሁለት አማራጮችን አቅርበዋል ።

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ግዛት የሚለው ቃል ይውጣ ወይም እንዳለ ይቀመጥ የሚለው አሁን የሀሳብ ልዩነት ስለሚታይበት በድምፅ እንዲወሰን ሀሳብ አቅርበው ግዛት የሚለው ቃል እንዳለ ይቀመጥ የሚለው ለድምፅ ቀርቦ 478 ድጋፍ ፣ 39 ተቃውሞ ፣ 9 ድምፀ ተአቅቦ ተመዝግቦ የፀደቀ ሲሆን በመጨረሻም አንቀጽ 2 እንዳለ እንዲፀድቅ ለድምፅ ቀርቦ 524 ድጋፍ ፣ 1 ተቃውሞ ፣ 5 ድምፀ ተአቅቦ ተመዝግቦ እንደለ ፀድቋል ።

ቀጥሎም አንድ ጉባኤ አባል ድምፅ ያልሰጡበትን ምክንያት ለመግለጽ ጠይቀው ስለተፈቀደላቸው አንቀጽ 2ን በተመለከተ ከቤቱ በርካታ የተለያዩ ሀሳቦች እንደተሰነዘሩ፣ ነገር ግን የውሳኔ ሀሳቡ አቀራረብ ከተሰጠው ሀሳብ የተዛባ መሆኑና የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን በዓለም አቀፍ ስምምነቶች መሠረት እንዲወሰን ተደንግጎ እያለ የጎሬቤት አገሮች በስም ተጠቅሰው አለመዘርዘራቸው ተገቢ ባለመሆኑ ድምፃቸውን እንዳቀቡ ገልጸዋል ።

ከዚያም ጉባኤው ለሻይ ዕረፍት ተነስቷል ።

ከሻይ ዕረፍት መልስ በኋላ የጉባኤው ሊቀመንበር በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ አንቀጽ 3 የኢትዮጵያ ሰንደቅ አላማ በሚለው ሥር ያሉትን ንዑሳን አንቀጾች በንባብ ካሰሙ በኋላ ጉባኤው ውይይቱን በእነዚህ ንዑሳን አንቀጾች ላይ እንደሚቀጥል አሳስበዋል ።

በዚሁም መሠረት አቶ ተፈራ መስተሌ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል በአንቀጹ አቀማመጥ ብዙም ችግር እንደሌለባቸው ጠቁመው ችግሩ ያለው የተለያዩ አካላት ለባንዲራው በሚሰጡት ትርጉምና ይዘት እንደሆነ ገልጸው በአገር አንድነትና በባንዲራ ስም በርካታ ብሔር / ብሔረሰቦች ወይም ሕዝቦች መብት ሲታፈንና ሲረገጥ ለዘመናት መቆየቱን ፣ አፄዎችና ደርጎች በባንዲራው እየማሉ ልጅ ያለአባት ፣ሚስት ያለባል ፣ እሮጊት ያለጧሪ ማስቀረታቸውን የሁሉም የቅርብ ጊዜ ትዝታ መሆኑን አስረድተዋል ።

አክለውም ከዚህ አኳያ ትኩረት መሰጠት ያለበት ለጉዝሩ ቀለሙ ወይም ለጨርቁ ሳይሆን ትርጉሙ ላይ መሆን እንዳለበት ፣ ባንዲራው በኢትዮጵያ የሚገኙ የብሔር/

ብሔረሰቦችን ወይም የሕዝቦችን እና የሃይማኖቶችን እኩልነት የሚያንፀባርቅ ብሔራዊ አርማ ሊቀመጥበት እንደሚገባ አስገንዝበዋል ።

ከዚያም በአንቀጽ 3 ንዑስ አንቀጽ 3 የተቀመጠው ክልሎች የራሳቸው ባንዲራና አርማ እንዲኖራቸው የሚገልጽ እንደሆነና እንደሚቀበሉት አመልክተዋል ።

በመቀጠልም አቶ ግርማ ታደሰ ክክልል 14 በአንቀጽ 3 ንዑስ አንቀጽ 1 የተቀመጡት የባንዲራው ቀለሞች ብዙም እንደማያነጋግሩ ፣ የኢትዮጵያ ብሔር ፣ ብሔረሰቦችና ሕዝቦች ባንዲራው የእኛ ነው በሚል ሊያከብሩትና ሊሞትለት የሚችሉት ብሔራዊ ማንነታቸው ሲጠበቅ ፣ ሰብአዊ መብታቸው ሲከበር ፣ ከሀገሪቱ ኢኮኖሚ መጠቀም ሲችሉና የሀብታቸው አዛዥ ሲሆኑ እንደሆነ ገልጸው በባንዲራው ስም የተደረገው አላስፈላጊ እልቂት መቀጠል እንደሌለበት ፣ በሕዝቦች ፈቃደኝነት ላይ የተመሠረተች ኢትዮጵያን ለመገንባት የብሔር/ብሔረሰቦችና የሕዝቦች እንዲሁም የሃይማኖቶች እኩልነት ሊኖር እንደሚገባ አስረድተዋል ።

አያይዘውም ለባንዲራው ይሰጥ የነበረውን ትርጉምና የሰብአዊ መብት ረገጣን በመቃወም አእላፍ ሕዝቦች ለትጥቅ ትግል መነሳታቸውንና መሞታቸውን ፣ ለባንዲራው ቀለም ይሰጥ የነበረው መለኮታዊ ትርጉምም ስህተት እንደሆነ ፣ የባንዲራውን ቀለም መለወጥ አስፈላጊ ቢሆን ኖሮ እያንዳንዱ የፖለቲካ ድርጅት ለትግል ይጠቀምበት የነበረውን አርማ በማንገብ እስከ አሁን ይቆይ እንደነበር ፣ ነገር ግን ፍሬ ነገሩ የባንዲራው ትርጓሜ በመሆኑ አሁንም ብሔሮች / ብሔረሰቦች እንዲሁም ሃይማኖቶች በእኩልነት የሚያስተሳስር አርማ እንዲኖር ማድረግና ትርጓሜውን በዚህ መለወጥ መቻሉ እንደሆነ ፣ ሕዝቦች የእኛ ነው ሊሉት የሚችሉትን ይህ አርማ ሊታከልበት ብቻ መሆኑን አስገንዝበዋል ።

በዚህም መሠረት አንቀጽ 3 ንዑስ አንቀጽ 2 ላይ የተቀመጠው አግባብ መሆኑን ጠቁመው አንቀጹ በሙሉ ባለበት መልኩ ቢቀመጥ እንደሚደግፉ አመልክተዋል ።

ቀጥሉም አቶ ታሪኩ ፅጌ ከክልል 14 ባንዲራን በተመለከተ በአንቀጽ 3 ንዑስ አንቀጽ 2 ላይ የብሔር /ብሔረሰቦችንና የሃይማኖቶችን እኩልነት የሚያረጋግጥ ብሔራዊ አርማ እንደሚኖር በሕገ መንግሥቱ መቀመጡ አግባብ እንደሆነና አንድነትን ለማምጣት እንደሚበጅና የባንዲራውን አተረጓጎም ካለፈው ትርጉም እንደሚለወጥ ገልጸው አንቀጹ በሙሉ እንደሚቀበሉት አስታውቀዋል ።

ከዚያም አቶ ግርማ ብሩ ከክልል 4 በሰንደቅ አላማና በባንዲራ መካከል ያለው ልዩነት ምን እንደሆነ ጠይቀው ልዩነታቸውን የሚያውቅ ካለ ሀሳብ በሚሰጥበት ጊዜ እንዲገልጽ መንገዱን እንዲያብራራ የጉባኤው ሊቀመንበር ቢያሳስቡም ምላሽ ሳይሰጥ ቀርቷል ።



በሌላ በኩል አቶ አዳሙ ደገፉ ከክልል 14 በውይይቱ ሂደት የአባቶቻችንና የአያቶቻችን ታሪክ እንዳይነሳ ገደብ እየተደረገ ቢሆንም ባንዲራውን ያስረከቡን ወርቅ ብለው እንዳልሆነ ፣ ባንዲራ የአገር መታወቂያ መለያ በመሆኑ ክብር እንዳለው ገልጸው ሕዝቡ ጨርቅ ብሎ እንደማይጠራው ፣ ሕዝቡ ባህር ፣ ተወካዮች አሳ ስለሆኑ ሕዝቡ እንዳይተፋቸው ተገቢውን የሕዝብ ፍላጎት ይዞ መራመድ እንደሚበጅ ፣ ከዚህ አኳያም በአንቀጽ 3 ንዑስ አንቀጽ 1 እና 3 ላይ ያሉት እንዳሉ ሆነው ንዑስ አንቀጽ 2 አስፈላጊ ስላልሆነ እንዲሰረዝ ሀሳብ አቅርበዋል ።

ቀጥሉም ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 የሰንደቅ አላማ ጉዳይ የኢትዮጵያ ሕዝብ በከፍተኛ ንቃት የሚከታተለው እንደሆነ ፣ በሰንድቅ አላማ ላይ የተለያዩ ብሔር ብሔረሰቦችና ሃይማኖቶችን የሚያንጸባርቅ ብሔራዊ አርማ እንዲሰፍር በተወካዮች ምክር ቤት ሲወሰን ሕዝቡ ብዙ ነገሮችን እንደተቸ ፣ በባንዲራ ስም ብዙ ግፍ ቢደርግም ብዙ መልካም ነገሮችም እንደተፈጸሙና ብዙዎችን ነፃ እንዳወጣ ፣ ለምሳሌ የወሎ እስላም አላይ ዋ አክበር ስላለ ምላሱ ሲቆረጥ እንደነበር ፣ ባንዲራው ወደ ደቡብ ከመዝለቁ በፊት አንድ ባላባት ሲሞት ሰባት ሰው ከነነፍሱ ይቀበር እንደነበር ፣ ሴት ልጆች ሲወለዱ ከነነፍሳቸው ይቀበሩ እንደነበር ፣ እነዚህን ድርጊቶች ባንዲራው እንዳስቀረ አመክልተው ደካማ ጎን ብቻ ሳይሆን ጠንካራ ጎኑም መጠቀስ እንዳለበት አብራርተዋል።

አያይዘውም እንደ ፈረንሳይ ፣ ጣሊያ የመሳሰሉ ያደጉ አገሮች በሰንደቅ አላማቸው ላይ ምንም ምልክት እንደሌለ ፣ ምልክቱ ባለመኖሩ በእነዚህ አገሮች ዲሞክራሲ የለም ማለት እንዳልሆነ ፣ ዲሞክራሲ የሚኖረው በሰንድቅ አላማ ላይ ምልክት በማድረግ ሳይሆን በአስተዳደር የብሔር / ብሔረሰቦች እኩልነት ሲጠበቅ መሆኑን ፣ ይህ ማለት በአንድ መንግሥት ሁለት ዓይነት አስተዳደር ሳይኖር ፣ የመንግሥት መሥሪያ ቤቶች በአንድ ብሔር ሳይያዙ ፣ ለአንዱ የተደረገው ለሌላው ሳይነፈግ ማለት እንደሆነ ጠቅሰው ዲሞክራሲ በወረቀት ላይ እንዲሰፍር ብቻ ሳይሆን እንደነ ማንዴላ ነጮች የፈጸሙብንን እርሱት ፣ እንደ የመን የርስ በርስ ጦርነት እርሱት በማለት ለወደፊት ሲታሰብ እንጂ አንዱ ብሔረሰብ በሌላው ላይ በመቀስቀስ ዲሞክራሲ ሊመጣ እንደማይችል አብራርተዋል ።

አክለውም የኢትዮጵያ ሰንደቅ አላማ በጠላት ዘመን በኤርትራ የነበራትን ክብር ገልጸው አንድነታችን የሚፀናው አንዱን ልጅ ሌላውን የእንጀራ ልጅ ማድርግ ቀርቶ ሁሉም እኩል ሲታይ መሆኑን አስገንዝበዋል ።

በመጨረሻም ከሰንደቅ አላማው ላይ አንድ ነገር ቢጨመር ወይም አንድ ነገር ቢቀነስ የኢትዮጵያ ሕዝብ እንደሚያዝንና ሕገ መንግሥቱንም እንደማይደግፍ ጠቅሰው ሕዝቡን የሚከፋፍለው የሽግግሩ መንግሥት እንደሆነ ጠቁመዋል ።

ከዚያም አቶ ሀሰን አሊ ከክልል 4 ባንዲራን በተመለከተ ሦስት አበይት ጉዳዮች እንዳሉ እነዚህም የባንዲራው ኅብረ ቀለማት ፣ የሕዝቦችን እኩልነት የሚያመለክት እንዲሁም የባንዲራው ኅብረ ቀለማት ፣ የሕዝቦችን እኩልነት የሚያመለክት አርማ መኖር ፣ እና ክልሎች አርማና ባንዲራ እንዲኖራቸው የሚሉት መሆናቸውን ጠቁመዋል ::

አያይዘውም በታሪክ የተለያዩ ገዢዎች የራሳቸው አርማ እንደነበራቸው ፣ አረንጓዴ ፣ ብጫ ፣ ቀይ ቀለም ያለው ባንዲራ ግን ተግባራዊ መሆን የጀመረው በአፄ ሚኒሊክ ዘመነ መንግሥት መሆኑን ጠቅሰው ግፍ ሲፈጸምበት የነበረው ሕዝብ በባንዲራው ነፃ ወጥቷል ተብሎ የተገለጸው አዲስ ፍልስፍና እንዳልሆነ ፣ አፍሪካን ተቀራምተው ሲገዟት የነበሩት ቅኝ ገዢዎችም የመጣናው ባርነትን ልናስወግድ ነው ፣ ሰብአዊ መብት ልናስከብር ነው ይሉ እንደነበር አስታውሰው ይህ አገላለጽ ከቅኝ ግዛት አስተሳሰብ የሚመነጭ እንደሆነ ሕዝቡ ሊገነዘበው እንደሚገባ ገልጸዋል ::

አክለውም ሁሉም አገሮች ባንዲራ እንዳላቸውና ሁሉም ግን ጨርቆች እንደሆኑ ፣ ማንሳት የሚፈለገው በባንዲራው ስም የደረሱትን በደሎች እንጂ የባንዲራውን ክብር አለመሆኑን ፣ ብዙ ግፍ ያደረሰውም ጨርቁ ሳይሆን ሥርዓቶች እንደነበሩ ፣ አሁንም የአባቶቻችንን ስህተቶች በማረም ፈንታ ምክንያት በመፍጠር ትክክለኛ አድርጎ ማቅረቡ አግባብ እንደዳልሆነ ጠቁመው የሕዝቦች መብት በዚህ ባንዲራ ሥር ታፍኖ እንደኖሩና አሁንም ደግሞ በዚህ ባንዲራ ሥር ነፃ እንደወጣ አስገንዝበዋል ::

ቀጥለውም ባንዲራው ላይ አንድም ነገር መጨመር ወይም መቀነስ የለበትም የሚለውን እንደሚቃወሙ ጠቅሰው ባንዲራው ላይ የብሔር ብሔረሰቦችና የሃይማኖቶች እኩልነት የሚያንፀባርቅ አርማ መታከሉንና የፌዴራሉ አባሎች የራሳቸውን ባንዲራና አርማ እንዲኖራቸው መደረጉን እንደሚደግፉ ገልጸዋል ::

ከዚያም አቶ አሊ አብዲ አሲ ከክልል 5 ኢትዮጵያን በተመለከተ ከዚህ ቀደም ምን ይወሳ እንደነበረ መዳሰስ እንደሚያስፈልግ ፣ የቀድሞዋ ኢትዮጵያ በጠመንጃ አፈሙዝ የተገነባች እንደነበረች ፣ በብሔሮችና በብሔረሰቦች መካከል ልዩነቶች እንደነበሩ ፣ አሁን አባቶቻችን እየተባሉ የሚነሱት የእርሳቸውን አባት የገደሉ እንደሆኑና በቤተሰባቸው የተነገራቸው ጨቋኝ አለ እየተባለ በመሆኑ የእርሳቸው አላማም ጨቋኝን ለመግደል እንደነበረ አስታውቀዋል ::

አክለውም የበፊቷ ኢትዮጵያ በሕዝቦቿ ፍላጎት የተገነባች ስላልነበረች አሁን ለወደፊት በኢትዮጵያውያን መካከል ወንድማማችነት እንዴት መስፈን አለበት ? በሚለው ላይ መወያየት እንደሚያስፈልግ ፣ በጣም የሚያሳዝናቸው ትክክል ያልነበረውን ታሪክ ትክክል እንደነበረ ተደርጎ ሲቀርብ መስማታቸው እንደሆነ ፣ ኢትዮጵያም የምትመሠረተው በሕዝቦቿ ፈቃደኝነት ላይ ነው ከተባለ የነበረው ሰንደቅ



አላማ መቀጠል እንደሌለበት ፣ የክልላቸው ሕዝብም ይህንን ባንዲራ ማየት ስለማይፈልግ ከደርግ ውድቀት በኋላ በመጀመሪያ ማቃጠል ይገባ እንደነበረ ፣ ምን ተፈርቶ ባንዲራው እንዲቀጥል እንዳልተደረገ እንደማያውቁ ፣ ኢትዮጵያ ውስጥ አሁን ያለው አስተዳደር በክልሎች የተደረጀ ስለሆነ ኢትዮጵያ የሚባለው ክልል 14 ብቻ ከሆነ እነሱው በባንዲራው ሊጠቀሙበት እንደሚችሉ ተናግረው ሆኖም ባንዲራው አብዮታውያን ኃይሎች እያከበሩት ስለሆነ ከሦስቱ ቀለማት በተጨማሪ ነጭ ቀለም ተደርጎበት እና የሽግግር መንግሥቱ አርማ በመሐሉ ታክሎበት እንዲቀጥል አሳስበዋል ::

ቀጥሉም ወ/ሮ አለማሽ ግርማይ ከክልል 1 ባንዲራው በመሠረቱ አርማ መሆኑን ፣ በባንዲራው ስም በአንዳንድ አካባቢዎች በተለይም በትግራይ ክልል ሳምረ በተባለ ቦታ በታጋዮች ሳይሆን በሰላማዊ ሰዎች ላይ ደርግ ጉዳት ማድረሱን ፣ በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ወይይት ወቅት ጨፍጫፊው ባንዲራው ሳይሆን ሰዎች እንደሆኑ እንደተገነዘቡና የባንዲራው ቀለም ሳይለወጥ በንዑስ አንቀጽ 2 ላይ የተቀመጠው ከታከለበት አንቀጹ እንዳለ እንደሚቀበሉት ገልጸዋል ::

ከዚያም አቶ ተቀባወርቅሰው አስረሱ ከክልል 3 አንቀጽ 3 ንዑስ አንቀጽ 1 ላይ ያለው እንዳለ እንዲቀመጥ ፣ ያለፈው ታሪክ በሚወሳበት ጊዜ ዕውነታውን ማስፈር አስፈላጊ እንደሆነ ገልጸው ባንዲራው የሕዝቦች ሳይሆን የገዢ መደቦች የመጨቆኛ መሣሪያ እንደነበር ፣ አሁን የምናዘጋጀው ባንዲራ ግን የሕዝቦችንና የሃይማኖቶችን እኩልነት በሚያረጋግጥ መልኩ መሆን እንዳለበት ፣ ይህም ሀሳብ እርሳቸውና የወከላቸው ሕዝብ እምነት መሆኑን አስታውቀው አንቀጽ 3 ንዑስ አንቀጽ 3 ባለበት መልኩ እንደሚቀበሉት አመልክተዋል ::

ቀጥሉም አቶ ዩሱፍ መሐመድ ከድር ከክልል 2 በየመጽሔቶች እንኳን የአፋር ሕዝብ ግመሉም ባንዲራውን ያውቀዋል ተብሎ ይጻፍ እንደነበር አስታውሰው በመሠረቱ የአፋር ሕዝብ ከስደትና ከጭንቀት ባንዲራው እንዳላዳነው ጠቁመው በባንዲራው ላይ ነጭ ምልክት እንዲቀመጥ ሀሳብ አቅርበዋል ::

ከዚያም የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ በአንድ በኩል ባንዲራው ባለፈው ታሪክ ሕዝቦችን ነፃ ያወጣ ፣ ከኋላ ቀርነትና ከጭቆና ያላቀቀ ፣ የአገር አንድነትን ያስጠበቀ ፣ ሕዝቦች በውስጣቸው ያለውን ኋላ ቀር አስተሳሰብ እንዥርደፍቁ ያደረገ ፣ በአጠቃላይ ያለፉት አባቶች ሕዝቡን በማስልጠንም ሆነ የሀገር ነፃነትን በማስጠበቅ የተገለገሉበት መሆኑ ሳይጎድፍና ምንም ሳይነካ እንዳለ መቀመጥ አለበት የሚል ሀሳብ መቅረቡን ፣ በሌላ በኩል ግን ባንዲራው መለያ እንደሆነና እስከ ዛሬ ድረስ አረንጓዴ ብጫ ፣ ቀይ ባንዲራ ለሕዝቦች ነፃነት የቆመ ሳይሆን ሕዝቦች የታረዱበትና

የተጨፈጨፉበት እንጂ ሕዝቦችን ነፃ ሲያወጣ አልታየም ፣ ከዚህም አኳያ ባንዲራው የሕዝቦችን ሉዓላዊነት፣ የብሔር / ብሔረሰቦችን መብት መገፈፊያ ሆኖ እንደቆየ ፣ ይህን እንጂ ይህንን ያደረገውና ሕዝቦችን የጨፈጨፉት የነበሩት ሥርዓቶች በመሆናቸው በባንዲራው ላይ የብሔር / ብሔረሰቦችንና ሃይማኖቶችን እኩልነት የሚያንፀባርቅ ብሔራዊ አርማ እንዲታከልበት የሚል ሀሳብ መቅረቡንና በሌላ በኩልም በባንዲራው ላይ ነጭ ርግብ እንዲጨመርበት የሚል ሀሳብ ማርቡን አብራርተዋል ::

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር በአንቀጽ 3 ላይ የበለጠ ውይይት ያስፈልገናል የሚል ካለ አስተያየት ማቅረብ እንደሚቻል ባሳሰቡት መሠረት በአንድ በኩል ወይይቱ ይቀጥል በሌላ በኩል በቂ ውይይት ስለተደረገበት ውይይቱ ቆሞ ድምፅ ይሰጥበት የሚሉ ሁለት ሀሳቦች ከቤቱ አቅርበው የጉባኤው ሊቀመንበር በሁለቱ ሀሳቦች ላይ ድምፅ እንዲጥ አድርገው ውይይቱ ይቀጥል የሚለው 285 ፣ ውይይቱ ይብቃ የሚለው 230 ፣ ድምፀ ተአቅቦ 1 ተመዝግቦ ጉባኤው በጉዳዩ ላይ በሚቀጥለው ቀን ውይይት እንደሚያድርግ ወስኖ ከቀኑ 07:10 የዕለቱ ውይት ተጠናቋል ::